# ምዕራፍ ፺

## አማች መሆን ይጠቅም ይሆን ?
## የወዳጆች ሙከራ

ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ፣ የጽሕፈትና የአገር ግዛት ሚኒስትር ሆነው በሚሠሩበት ጊዜ፣ ከንጉሠ ነገሥቱ ሴት ልጅ ከልዕልት ተናኘወርቅ ኃይለሥላሴ ጋር ጋብቻ እንዲፈጽሙ ታስቦ እንደነበርና፣ ኋላም በምን ምክንያት ሳይሣካ እንደቀረ ሲነገር የቆየውን የአፍ ታሪክ ብዙ ሰዎች ያስታውሳሉ። በመሠረቱ ይህ የጽሑፍ ሰነድ የሌለው ዜና ሲወራ፣ አተራረኩና አቀራረቡ በተለያየ መንገድ ይሁን እንጂ፣ ታስቦበት ነበር የተባለው ጋብቻ እውነት አይደለም ማለት አይቻልም።

ከዚህ በፊት እንደተነገረው፣ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ በኢት. አቆ. በ1935 ዓ.ም የጽሕፈት ሚኒስትርነቱን እንደያዙ አገር ግዛትን ሲደርቡ፣ ሥልጣናቸው ምን ያህል እንደተስፋፋ በግልጽ የሚታይ ከመሆኑም በላይ፣ ከንጉሠ ነገሥቱ ጋር ያላቸው ቅርበትና ባለሟልነት፣ መጠኑን ለመለካት ከማይቻልበት ሁኔታ ደርሶ ነበር። በዚህ ጊዜ፣ በጸሐፊ ትዕዛዝ ላይ ጥላቻ ያደረባቸው አንዳንዶቹ ሚኒስትሮች፣ ኧረ ለመሆኑ የዚህ ሰው የሥልጣን አያያዝ ከመንበረ መንግሥቱ ጉልላት አልተጠጋም ወይ? የዚህ ሁሉ መጨረሻው ምንድን ነው? እያሉ ሲተቹ፣ በወልደጊዮርጊስ አመራርና ብልህነት እናምናለን የሚሉት ወዳጆች ደግሞ፣ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ የጠቅላይ ሚኒስትርነቱን ሥልጣን ቢሰጧቸው፣ የአገራችንን አስተዳደር ምን ያህል ባራመዱት ነበር? በማለት ምኞታቸውን ሲያፋፍሙ ይታዩ ነበር። ቀዳማዊ ኃይለሥላሴም ስለ ወልደጊዮርጊስ የሚታሰበውን የሁለት ወገኖች፣ ማለት የደጋፊዎችና የተቃዋሚዎች አስተያየት ምንና ምን እንደሆነ ቢሰሙም፣ አንዳች እርምጃ ሳይወስዱ የራሳቸውን የፖለቲካ ጨዋታ እያካሄዱ መቆየትን መረጡ። ይኸውም፣ የወልደጊዮርጊስን የቅርብ ባለሟልነት በማሳየት፣ ጠንካራ ሠራተኛነታቸውንም በአደባባይ በመግለጥ፣ አብዛኛውን ጊዜ አጥንተው የሚያቀርቡላቸውንም ሐሳብ ተቀብለው በመፍቀድ ደስ ቢያሰኟቸውም፣ ወደ ጠቅላይ ሚኒስትርነት ደረጃ ለማሻገር ፍላጎት ያላቸው ወይም የሌላቸው መሆናቸውን ማሳወቅ አልፈለጉም። ወልደጊዮርጊስ ጠቅላይ ሚኒስትር መሆን አለባቸው በማለት የራሳቸውን ቁርጥ ውሳኔ ያደረጉት ደጋፊዎች፣ ሐሳባቸው ከግቡ ሊደርስ የሚችለው፣ ንጉሠ ነገሥቱ ልጃቸውን ልዕልት ተናኘወርቅ ኃይለሥላሴን ለጸሐፊ ትዕዛዝ በመዳር አማቻቸው ሲያደርጓቸው ነው የሚል ዕምነት አደረባቸው። በ1903 ዓ.ም መጨረሻ ላይ የደጃዝማች ተፈሪ መኰንን እና የወይዘሮ መነን አስፋው ጋብቻ ከተፈጸመ በኋላ፣ በጥቅምት 1905 ዓ.ም የተወለዱት የመጀመሪያዋ ሴት ልጅ ተናኘወርቅ፣ የሲዳሞ ጠቅላይ ገዥ የራስ ደስታ ዳምጠው ባለቤት የነበሩ ናቸው። የስድስት ልጆቻቸው አባት የሆኑት ራስ ደስታ በአጋዴን ጦር ሜዳ ላይ በፋሽስት ጣልያን ከተገደሉ በኋላ፣ ልዕልት ተናኘ ወርቅ ኃይለሥላሴ ሌላ ትዳር ሳይዙ ወላጆቻቸው ዘንድ ይኖሩ ነበር። ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስም ከጃንሆይ ጋር በስደት ከኖሩበት ከእንግሊዝ አገር ሲመለሱ፣ የሕግ ባለቤታቸውን በሕይወት ባለማግኘታቸው የሚኖሩት ብቻቸውን ነው።

የወልደጊዮርጊስ ወዳጆች ይህ ጋብቻ የተቀደሰ ሆኖ ለአገር ጥቅም የሚሰጥ ይሆናል በማለት ሐሳቡን ሲቀይሱ፣ የተመረኮዙባቸውን ሁለት ዋና ዋና ምክንያቶች ደርድረዋል።

እነዚህም፡-

፩ኛ/ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ገና ከጣልያን ጦርነት በፊት ወልደጊዮርጊስን በሥራ አሳድገው ለከፍተኛ ኃላፊነት ሲያበቋቸው፣ የሚጠበቅባቸውን አገልግሎት እስከዛሬ በትክክል የፈጸሙና በመፈጸም ላይ የሚገኙ ስለሆኑ፣ በአሁኑ ሰዓት በዙሪያቸው ካሉት ታላላቅ ሰዎች መካከል ለአማችነት ከጸሐፊ ትዕዛዝ የተሻለ ሰው አይታይም።

፪ኛ/ ወልደጊዮርጊስ ብልህና ጠንካራ የሥራ መሪ ከመሆናቸው በላይ፣ ለጃንሆይ ፍጹም ታማኝነታቸውን ስለአስመሰከሩ፣ የኢትዮጵያን አስተዳደር ለማሻሻልና የወደፊቱንም የዘውድ አገዛዝ በጠነከረ መሠረት ላይ ገንብቶ ለትውልድ እንዲተላለፍ ለማድረግ፣ ከጸሐፊ ትዕዛዝ የተሻለ ጠቅላይ ሚኒስትር ይገኛል ማለት አይቻልም።

በዚህ አስተሳሰብ ላይ የተወጠነውን ዕቅድ ከግቡ ለማድረስ፣ የወልደጊዮርጊስ ወዳጆች ለቤተ መንግሥቱ ቅርበት ካላቸው ከጠቅላይ ገዥዎች፣ ከሚኒስትሮችና ከቤተክህነት መሪዎች መካከል እየመረጡ በመመካከር ላይ መሆናቸው በተሰማ ጊዜ፣ ንጉሣውያን ቤተሰቦቹ ተባብረው በብርቱ ለመቃወም ተነሡ። በታላቁ መስፍን በልዑል ራስ ካሣ ኃይሉ በዚያን ጊዜ የዘውድ ም/ቤት ፕሬዚዳንት መሪነት፣ ልዑል አልጋወራሽ አስፋወሰን፣ ልዑል መኰንን የሐረር መስፍን፣ ልዕልት የሻሸወርቅ ይልማና ባለቤታቸው ጠቅላይ ሚኒስትር መኰንን እንዳልካቸው በተገኙበት ስብሰባ ተደርጐ፣ ለወልደጊዮርጊስ ስለሚታሰበው ጋብቻ <u>አስተያየት ተሰጠበት</u>[*]። በዚሁ ጊዜ ከራስ ካሣ የተገለጸው አስተያየት የሚከተለው ነበር። " .... ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ በዚያ በመከረኛው የጣልያን ዘመን፣ ለንጉሡ ነገሥቱ ያለውን ታማኝነትና ለአገሩም ያለውን ፍቅር በሚገባ ያስመሰከረ ስለሆነ፣ በዚህ በኩል ምንም ዓይነት እንከን አይገኝበትም። ነገር ግን፣ ከነፃነት መመለስ በኋላ በጸሐፊ ትዕዛዝነቱና በአገር ግዛት ሚኒስትርነቱ የሚያሳየው የሥልጣን አጠቃቀም በየጊዜው እየናረ ስለሄደ፣ መቆሚያው የት ላይ እንደሚሆን ማወቅ አይቻልም። በአንዳንድ ረገድ እንደተረዳነውም እኛን የንጉሣዊውን ቤተሰቦች ጨርሶ አይወድም። አልፎ አልፎም ከሚናገረው እንደሚሰማው፣ መሳፍንትና መኳንንት የሚባለውን ወገን፣ በተለየም የጨዋ ልጅ የሚባለውን ከጥንት ሲያያዝ የመጣ ወግ ከልቡ ይቃወማል ይባላል። ቢቸግረኝ፣ አንድ ቀን ጸሐፊ ትዕዛዝን ላነጋግርህ እፈልግሃለሁ ብዬ ጠራሁት።

..... የጨዋ ልጆች የሚባሉትን ሁሉ እንደምትጠላቸው በሰፊው ይነገራል። አንተ የጃንሆይ ዋና ረዳት የሆንክ ሰው ይህ ጥላቻ ለምን እንዳደረብህ ሊገባኝ አልቻለም። ምናልባት ባታውቀው ይሆናል እንጂ፣ ወደፊት ያንተም ልጆች እኮ፣ የጨዋ ልጆች ከመባል አያመልጡም። በባህላችን፣ የጨዋ ልጆች የሚባሉት ሁሉ

---

[*] ከብሪጋድየር ጄኔራል መኰንን ደነቀ ዋና የእልፍኝ አስከልካይ የተገኘ

ንጉሥ ከሾማቸውና ከአሳደጋቸው ታላላቅ ሰዎች የተወለዱና በሥርዓት ያደጉት ናቸው። አንተም የንጉሠ ነገሥቱን ከፍተኛ ሹመትና ኃላፊነት በመቀበልህ ቁጥርህ የግዴታ ከታላላቅ ሰዎች መካከል ሆኗል። በዚህም አኳኋን ያንተም ልጆች ከጨዋ የተወለዱ ናቸው። ይህንን መካድ አትችልም ብዬ ነገርኩት። ..... ይህንን ስነግረው ማለፊያ በሆነ መንፈስ እንዳዳመጠኝ አስታውሳለሁ። ነገር ግን፣ ሐሳቤን ተቀብሎ የሚያሻሽል ነው ብዬ አልጠበቅኩም። በልማድ እንደምናውቀው አንዳንድ ጊዜ በሰዎች መካከል የሚፈጠር መጠላላት፣ በቤተሰብ ትልቅነትና በቤተሰብ ተራነት ልዩነት ላይ የተመሠረተ ከሆነ፣ አንዱ አንዱን አላሸነፈ ድረስ፣ በሰላም የሚገኝ ፍቅር የለም። ወልደጊዮርጊስም፣ ምንም ጃንሆይ ቢመርጡትና ባለሟል ቢያደርጉት፣ በሥልጣን ቢያሳድጉትና በሀብትም እንዲበለጥግ ዕድሉን ቢሰጡት፣ ያችን በልጅነቱ ያደገባትን በታላላቅ ቤተሰብ ተወላጆች ላይ ያሳደረውን ጥላቻ ምንጊዜም አይፍቃትም። ለዚህም ምሳሌ የሚሆነው፣ ጃንሆይ በሰጡት ትልቅ ሥልጣን፣ ለንጉሠ ነገሥቱ ከፍ ያለ አገልግሎት ማበርከቱ የማይታበል ቢሆንም፣ ይወደኛል የሚለውን ወገን ሲጠቅምና ይጠላኛል ብሎ የሚያስበውን ሲያጠቃ ስለሚታይ፣ ዳኝነቱ ሁልጊዜ ያጋደለ ነው። በተጨማሪም፣ በዚህ በልጅነቱ ባደገበት ቂመኛ በሆነው መንፈሱ እኛን በመልካምና በጤና የሚያስበን አለመሆኑን እናውቃለን። አሁን ደግሞ በዚህ ሁሉ በያዘው ሥልጣን ላይ አማቻችን ሆኖ ከቤተመንግሥቱ ከገባ፣ ምን እንደሚያደርስ መገመት ስለሚቻል ጃንሆይ እንዲያሰቡበት መድከም አለብን .... "

ከራስ ካሣ በኋላ፣ ከጠቅላይ ሚኒስትሩ ከቢትወደድ መኰንን እንዳልካቸው የቀረበው አስተያየት የሚከተለው ነበር። " .... የጃንሆይ የቅርብና ታማኝ አገልጋዮች ናቸው ከሚባሉት ሚኒስትሮች መካከል፣ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስና አቶ መኰንን ሀብተወልድ፣ በመሳፍንትና በመኳንንት ቤተሰቦች ላይ ያላቸው የግል ጥላቻ የተደበቀ ምሥጢር አይደለም። አንድ ጊዜ፣ ጃንሆይ ሦስታችንንም (እኔ ጸሐፊ ትዕዛዝ መኰንን) አንድ ጉዳይ አጥንተን እንድናቀርብላቸው አዘውን፣ በተሰበሰብንበት የመሥሪያ ጠረጴዛ ላይ፣ የኢትዮጵያ መሳፍንትና መኳንንት ለአገር ዕድገት እንቅፋቶች ናቸው በማለት አቶ መኰንን ሀብተወልድና ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ እየተደጋገፉ የተናገሩትን መቼውንም አልረሳውም። እነዚህ ሁለቱ ሚኒስትሮች፣ በግል ወዳጅነት ተሳስረው ማን ይነካናል ? እስከ ማለት የደረሱ በመሆናቸው፣ መታረም ያስፈልጋቸዋል ብዬ ለጃንሆይ አመልክቼ ነበር። እስካሁን እንደማየው፣ እነዚህ ሰዎች ጨርሶ አልተሻሻሉም። እንዲያውም እየባሰባቸው የሄዱ ይመስለኛል። አሁን ደግሞ በጣም የተገረምኩት፣ የጸሐፊ ትዕዛዝ ወዳጆች፣ በጋብቻ የንጉሠ ነገሥቱ አማች እንዲሆንላቸው በሚያደርጉት ሙከራ ነው። ምክንያቱ ምንድን ነው ? ተብሎ ቢጠየቅ፣ በጋብቻ ተቀላቅለን የምንፈልገውን ሁሉ እናገኛለን በሚል ጥቅም ላይ የተመሠረተ ካልሆነ በስተቀር፣ ለሌላ ለበጐ ምግባር የታሰበ እንዳልሆነ የተረጋገጠ ነው። በአሠራሩ እንደምናየውም፣ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወዳጆቹን በወረንጦ እየለቀመ፣ በሹመት በማሳደግ የደጋፊዎቹን ቁጥር በማበርከት ላይ ነው። ለዚህም ዋና ረዳቱ አቶ መኰንን ሀብተወልድ ለመሆኑ የታወቀ ነው። በዚህ አኳኋን የእነዚህ የሁለት ሰዎች (የወልደጊዮርጊስና የመኰንን) ሁኔታ የሚያሳስብ ስለሆነ፣ መድኃኒቱ ተፈልጐ መገኘት አለበት። .... ወደ ዋናው ጉዳይ ልመለስና፣ ልዑል ጌታዬ እንደአሉት፣ ጸሐፊ ትዕዛዝ ምንም እንኳ ከዚህ ቀደም ያበረከተው አገልግሎት ሊታሰብለት ይገባል ቢባልም፣ ዛሬ ከተሰጠው ከፍተኛ ደረጃና ሥልጣን አልፎ አማች ሆኖ ሲመጣ፣ በተለይ ስለ እኔ መልካም አያስቡም ነበር በሚላቸው በንጉሣዊ ቤተሰቦች ላይ ለመበቀል ወደ ኋላ እንደማይል መታሰብ አለበት። እርግጥ ነው ! ጃንሆይ እያሉልን እንዴት ይህ ሁሉ ሊደርስ ይችላል ? ተብሎ ይታሰብ

ይሆናል። በዓለም ታሪክ ደርሶ እንደታየው፣ ነገሥታቶች ብዙ ጊዜ ከምንም አንሥተው በሹመት ለከፍተኛ ደረጃ ያበቋቸውን አገልጋዮቻቸውን በጣም ስለሚያምኗቸው፣ ከአማካሪዎቻቸው ምንም ዓይነት አስተያየት ቢቀርብላቸው ለጥቅማቸው በደል ይፈጽማሉ ብለው አይጠረጥሯቸውም። ነገር ግን፣ ነገሥታቶቹ ራሳቸው እነዚህ ታማኞቻቸው በሥልጣን ሲወሰልቱ ባገኟቸው ጊዜ፣ ከብዙ ዘመን ጀምሮ በአስተዳደሩ ላይ ያደረሱትን ጉዳት ለመጠገንና ለማስተካከል የረዥም ጊዜ ድካም እንደጠየቃቸው ይነገራል። አሁንም ሁላችንም እንደምናየው፣ ጸሐፌ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ከወዳጁ ከአቶ መኰንን ሀብተወልድ ጋር ሆኖ የወደደውንና የሚጠላውን እየለየ የፈለገውን በማድረግ ላይ ስለሚገኝ፣ በዚሁ እንዲቀጥል ጊዜ ከተሰጠው፣ የሚፈጽማቸውን በደሎች በመጨረሻው መጠናቸውን መለካት ከማንችልበት ደረጃ እንደምንደርስ በበኩሌ የሚሰማኝን አመለክቻለሁ። የጸሐፌ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ አደገኛነቱ፣ አማችነቱ ብቻ ሳይሆን፣ በሥልጣን መቆየቱ ጭምር ስለሆነ፣ የወዳጁም የአቶ መኰንን ሀብተወልድ ጉዳይ አብሮ መወሰን እንደሚኖርበት አሳስባለሁ ….. "

## የራስ ካሣ የማጠቃለያ አስተያየት

ቢትወደድ በተናገርከው ውስጥ ዓቢይ ጉዳያችን ስለሆነው ስለጋብቻው ብቻ ሳይሆን፣ የጸሐፌ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስና የአቶ መኰንን ሀብተወልድ በወዳጅነት መተሳሰር አሥጊነቱን አጠንክረህ አመልክተሃል። አንተ ስለዚህ ጉዳይ ስትናገር፣ አንድ በቀድሞ ዘመን የደረሰ ታሪክ ትዝ አለኝ። አንድ ባለሞያ የሆነ ትልቅ ጌታ ካሉት አገልጋዮቹ መካከል፣ ገብረእግዚአብሔርና ገብረክርስቶስ የተሰኙት ፍቅራቸው ጠንቶ በሥራቸው ላይ ሲረዳዱና ሲደጋገፉ፣ በጉርብትና የሚኖር አንድ ወዳጅ በአንክሮ ይመለከታል። አንድ ቀን ይኸ ጉረቤት ዋናውን ባለቤት ያገኝና፣ ጌታ ሆይ? እነዚህ ሁለቱ አገልጋዮችህ (ገብረእግዚአብሔርና ገብረክርስቶስ) እጅግ ተግባብተውና ተዋደው እየተረዳዱ ሲያገለግሉህ አይቼ በጣም ተደሰትኩ ይለዋል። ጌታው ሲመልስ፣ አዬ ! ወዳጄ፣ ለእኔስ የሚጠቅመኝ ከሚዋደዱ እየተጣሉ አንዱ አንዱን ቢጠብቅልኝ ነበር ብሎ መለሰለት ይባላል። ….. አሁንም፣ ከጃንሆይ ሚኒስትሮች ውስጥ ሁለቱ፣ ወልደጊዮርጊስና መኰንን እየተደጋገፉ መሥራታቸው ጉዳት ያስከትላል ? ወይስ ተለያይተው በየፊናቸው ቢያገለግሉ ይጠቅማል ? ይህንን መዝነው የሚሻላቸውን የሚወስኑት ራሳቸው ጃንሆይ መሆን አለባቸው። ደግሞም የእነዚህ ሰዎች ወዳጅነትና መቀራረብ እስከ ዛሬ ድረስ ከጃንሆይ አመለካከት የተሠወረ ነው ማለት አይቻልም። በዚህ ጉዳይ የእኔን ሐሳብ ማወቅ ከፈለግህ፣ መኰንን ሀብተወልድን አሥጊ ሰው አድርጌ አላየውም። ቢመቸውም፣ ባይመቸውም፣ ለጃንሆይ ታማኝነቱን ያዛንፋል ብዬ አላስብም። ወልደጊዮርጊስ ግን፣ ከተመቸውና የሥልጣኑ ኃይል ካደፋፈረው፣ ጃንሆይን ለማስቸገር የሚያመነታ አይመስለኝም። ስለዚህም ነው፣ የወልደጊዮርጊስ ወዳጆች የሚያስቡትን የጋብቻ ጉዳይ አንቀበልም የምንለው። በጠቅላላው ሁላችንም ሐሳባችንን ገልጠን በማሠሪያው ተስማምተንበታል። አሁን የሚቀረን ለጃንሆይ አቅርበን ማስረዳት ብቻ ነው ….. " ሲሉ፣ የዘውዱ ምክር ቤት ሊቀመንበርስ ውሳኔያቸውን ሰጡ።

ስለ ልዕልት ተናኘወርቅና ጸሐፌ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ የጋብቻ ዕቅድ በአፍ ታሪክ የሚነገረው ብዙ ሲሆን፣ ከእነዚህም ውስጥ ተስፋፍቶ የሚወራው፣ ጸሐፌ ትዕዛዝ የጃንሆይ አማች እንዳይሆኑ ተቃዋሚዎቻቸው የጠነከሩት፣ የድሀ ወገን በመሆናቸው ነው እየተባለ ነው። የዚህ መጽሐፍ ደራሲ ባደረገው ምርምር ዋናው

ምክንያት፤ የዘር ጉዳይ ሆኖ አላገኘውም። የቤተ መንግሥቱ ታሪክ እንደሚያሳየው፤ ከወልደጊዮርጊስ በፊት ሆነ ከወልደጊዮርጊስ በኋላ፤ የንጉሠ ነገሥቱ አማቾች ከሆኑት ሰዎች መካከል አንዳንዶቹ በትውልዳቸው ከወልደጊዮርጊስ የተለዩ ወይም የሚበልጡ አልነበሩም። በዚያን ጊዜ የተደረገው ተቃውሞ በዘር ድህነት ላይ የተመሠረተ ቢሆን ኖሮ፤ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ልጃቸውን ለጸሐፊ ትዕዛዝ ለመዳር አይቸገሩም ነበር። ነገር ግን፤ እጅግ በተከበሩት መስፍን በልዑል ራስ ካሣ መሪነት ንጉሣዊው ቤተሰብ ብርቱ ተቃውሞ ያደረገው፤ አጅሬ ወልደጊዮርጊስ አማች ሆነው ከቤተመንግሥቱ ከገቡ፤ በሥልጣን ዘውድ ቀረሽ ንጉሥ ሆነው፤ እንኳንስ ለቤተሰቦቻቸው፤ ለራሳቸው ለንጉሠ ነገሥቱም ያሠጋሉ የሚለውን ፍራቻ በማጥበቅ ነው።

ቀዳማዊ ኃይለሥላሴም ይህን ከቤተሰባቸው የቀረበላቸውን የተቃውሞ ሐሳብ ሲመለከቱ፤ ጋብቻውን ለመፈጸም የሚቻል ሆኖ አላገኙትም። ሐሳቡን የጸነሱት የወልደጊዮርጊስ ወዳጆችም ጃንሆይ የገጠማቸውን ችግር በመረዳትና፤ ከንጉሣዊው ቤተሰቡም ጋር መታገሉ አይጠቅምም በማለት፤ ጉዳዩ ይፋ ሳይወጣ እንዲሁ ተድበስብሶ እንዲቀር አደረጉ። ከወልደጊዮርጊስ ወዳጆች መካከል፤ በጣም ቅርብና ትልቅ የሆኑት አቶ መኰንን ሀብተወልድ፤ በዚህ በንጉሣዊው ቤተሰብ ጋብቻ ጉዳይ በሐሳቡም ሆነ በምክሩ ተካፋይ እንዳልነበሩ ታውቋል። የታሰበው ሊፈጸም አለመቻሉን ሲሰሙ፤ ለወዳጃ ለጸሐፊ ትዕዛዝ የሕይወት ጓደኛ የምትሆነውን ፈልጌ የምድረው እኔ ነኝ በማለት፤ መኰንን ሀብተወልድ ቆርጠው ተነሱ።

## ጸሐፊ ትዕዛዝ ትዳር ያዙ

ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ ከንጉሠ ነገሥቱ ጋር እንደ ኢት.አቆ. ሚያዝያ 27 ቀን 1933 ዓ.ም አዲስ አበባ ሲገቡ፤ ምንም እንኳ የኢትዮጵያ ነፃነት በመመለሱ እጅግ የተደሰቱ ቢሆንም፤ በቤተሰቦቻቸው ላይ ያጋጠማቸው ሀዘን ቀላል አልነበረም።

- አባታቸውንና ወንድማቸውን ፋሽስት ገድሎባቸዋል፤
- ሴት ልጃቸው ሠናይት ወልደጊዮርጊስ በሕመም ሞታለች፤
- ባለቤታቸው (የአምስቱ ልጆቻቸው እናት) ወይዘሮ ከትነሽ ወልደማርያም፤ ወልደጊዮርጊስ ሱዳን ከደረሱ በኋላ የኢትዮጵያ ነፃ መውጫ ድርጅት በሚዘጋጅበት ጊዜ በሕመም ከዚህ ዓለም በሞት ተለይተዋል።

ከአምስት ዓመት ስደት በኋላ ወልደጊዮርጊስ አዲስ አበባ ሲገቡ ያጋጠማቸውን ይህንን ሁሉ ኃዘን ለመቋቋምና የወደፊት ሕይወታቸውን ለመገንባት የአምስት ዓመታት ጊዜ ወስዶባቸዋል። ወዳጃቸው አቶ መኰንን ሀብተወልድ ለጸሐፊ ትዕዛዝ የምትሆን ደህና የሕይወት ጓደኛ ፈልጌ ማግኘት አለብኝ ብለው ባደረጉት ጥረት መሠረት፤ የግራዝማች ይልማ ነከሬ ልጅ የሆኑትን ወይዘሮ አልማዝ ይልማን መረጡላቸው። አባታቸው ግራዝማች ይልማ በቤተመንግሥቱ "ባሻ ዣግሬ" ሆነው ያገለገሉና ለንጉሠ ነገሥቱም ቅርብ እንደነበሩ ከቤተሰባቸው የተገኘው መረጃ ያመለክታል። ግራዝማች ይልማ፤ ጠላት ኢትዮጵያን በወረረ ጊዜ በጃንሆይ ትዕዛዝ ደጃዝማች በየነ መርዕድ በባሌ በኩል በሚመሩት ጦር ውስጥ ተደልድለው ሲዋጉ፤ በመጨረሻ በጠላት ተይዘው ብዙ ሥቃይ ከደረሰባቸው በኋላ የተገደሉ ናቸው።

የግራዝማች ይልማ ሦስተኛዋ ሴት ልጅ የሆኑት ወይዘሮ አልማዝ፣ የኢትዮጵያ ነፃነት ከተመለሰ በኋላ አዲስ አበባ ወደ ራስ መኰንን ድልድይ በሚወስደው ጉዳና ላይ፣ መኰንን ሀብተወልድ ባቋቋሙት ዘወትር ለሕዝብ የሚታይ የእርሻና የኢንዱስትሪ ምርት ኤግዚቢሽን ውስጥ ተቀጥረው ይሠሩ ነበር። ወይዘሮ አልማዝ በዚያን ጊዜ ዘመናዊውን አለባበስ የሚከተሉና በንቃት ራሳቸውን የሚጠብቁ፣ የተመደቡበትን ሥራ በትክክል የሚፈጽሙ፣ የሥራ ሰዓታቸውን የሚያከብሩ ጨዋ ሴት በመሆናቸው፣ አቶ መኰንን ሀብተወልድ ለወዳጃቸው ለጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ በዚያን ጊዜ የጽሕፈትና የአገር ግዛት ሚኒስትር፣ የትዳር ጓደኛቸው እንዲሆኑ መረጡላቸው። ጸሐፊ ትዕዛዝም በዚሁ ተስማምተው ሐምሌ 14 ቀን 1938 ዓ.ም ጋብቻቸው ተፈጸመ። ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ከወይዘሮ አልማዝ ይልማ ጋር ለሠላሳ ዓመታት አብረው በኖሩበት ዘመን፣ አንድ ሴት ልጅና ሦስት ወንዶች ልጆች አፍርተዋል።



ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ እና ወ/ሮ አልማዝ ይልማ
በኢት.ቀ ሐምሌ 14 ቀን 1938 ጋብቻቸውን ፈጸሙ፤

# ምዕራፍ ፰

# የአጅሬ ወልደጊዮርጊስ
# የሥልጣን ኃይል

በአፄ ምኒልክ ዘመነ መንግሥት በኢትዮጵያ ታሪክ ለመጀመሪያ ጊዜ የተመሠረተውን የጽሕፈት ሚኒስትርነትና የጸሐፊ ትዕዛዝነትን ማዕረግ የተሾሙት፡-

1ኛ/ ጸሐፊ ትዕዛዝ ገብረሥላሴ ወልደ አረጋይ
2ኛ/ ጸሐፊ ትዕዛዝ አፈወርቅ ወልደ አረጋይ
3ኛ/ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደ መስቀል ታሪኩ
4ኛ/ ጸሐፊ ትዕዛዝ ኃይሌ ወልደሩፋኤ ሲሆኑ

አምስተኛው ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ ናቸው፡፡ እነዚህ አምስቱም ጸሐፊ ትዕዛዞች የተመረጡት በችሎታቸው እንጂ፤ አንዳንድ ሰዎች እንደሚሉት ቡልጋ ጸሐፊዎች የሚመረቱባት አገር ስለሆነችና ተሿሚዎቹም ቡልጉች መሆን አለባቸው ተብሎ አይደለም፡፡ ስለአሿሿማቸው በተደረገው ጥናት፤ ሁሉንም ለዚህ ከፍተኛ ደረጃ ያስመረጣቸው በየግላቸው ያላቸው ችሎታ እየተመዘነ መሆኑ ታውቋል፡፡

በጸሐፊ ትዕዛዞቹ የሹመት ቅደም ተከተል አምስተኛውን ደረጃ የያዙት፤ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ፤ ከእሳቸው በፊት ከነበሩት ከአራቱ ሰዎች የበለጠ ዘመን የሠሩና የበለጠ ሥልጣን የነበራቸው መሆናቸውን እናያለን፡፡ ከፋሽስት ጣልያን ይዞታ የኢትዮጵያ ነፃነት ከተመለሰ በኋላ፤ ከግንቦት 7 ቀን 1933 ዓ.ም እስከ ሚያዝያ 17 ቀን 1947 ዓ.ም ድረስ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ፡-

ሀ/ ለሁለት ዓመታት የጽሕፈት ሚኒስትር - 1933-1935

ለ/ ለስድስት ዓመታት የጽሕፈትና የአገር ግዛት ሚኒስትር - 1935-1941

ሐ/ ለስድስት ዓመታት የጽሕፈትና የፍርድ ሚኒስትር - 1941-1947

ሆነው፤ በድምሩ ለአሥራ አራት ዓመታት በቆዩበት ዘመን፤ በሥልጣናቸው በሚገባ ሠርተውበታል፡፡ በብዙ ሰዎች ዘንድ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስን "አጅሬ" የሚል ቅጽል ያሰጣቸው፤ ደፋርና ልበ ሙሉ፤ በሥልጣናቸው መቶ በመቶ የሚጠቀሙ፤ የሚፈልጉትን ከግቡ ከማድረስ ወደ ኋላ የማይሉ፤ እንኳንስ ቀጥታ በሚመለከታቸው መሥሪያ ቤቶች ጉዳይ ቀርቶ፤ የሌሎቹንም ሚኒስቴሮች ሥራ በንጉሠ ነገሥቱ ስም እየተከታተሉ፤ በትጋት ሠርቶ ፍሬ የሰጠውንና በስንፍና የሚያጓድለውን የሚያጋልጡ በመሆናቸው ነበር፡፡

በዚያን ዘመን በንጉሠ ነገሥቱ ዘንድ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ፤ የነበራቸውን ተወዳጅነት፣ ታማኝነትና ተደማጭነት፣ ከመኮንን ሀብተወልድ በስተቀር የሚወዳደራቸው ሌላ ሰው አልነበረም፡፡ መኮንን እና ወልደጊዮርጊስም፤

በንጉሠ ነገሥቱ የተወደዱና ሙሉ ዕምነት የተጣለባቸው ባለሟሎች በመሆናቸው፤ እርስ በርሳቸው ፍጹም በሆነ መግባባት ጃንሆይን በቅን ከማገልገልና ከመጠበቅ በስተቀር፤ እንደ አንዳንድ ባለሥልጣኖች በመካከላቸው መቀናናትና መፎካከር አልታየባቸውም።

ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ከስደት እንደተመለሱ፤ ወልደጊዮርጊስን መጀመሪያ የጽሕፈት ሚኒስትር ካደረጓቸው በኋላ፤ በሁለት ዓመት ጊዜ ውስጥ በያዙት ሚኒስቴር ላይ የአገር ግዛት ሚኒስትርነትን ደርበው ሲሾሟቸው፤ በተለይ መሳፍንትና መኳንንት ያልተደሰቱ መሆናቸው ታውቋል። ይሁን እንጂ፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስም ከጽሕፈት ሚኒስትርነት ጋር አገር ግዛትን ከጨመሩ በኋላ፤ የተደሰተም ቢኖር የተከፋ፤ የያዙትን ሥልጣን በተግባር ለማሳየትና በብዙዎች ሰዎች ዘንድ "አጅሬ" ተብሉ የተሰጣቸውን የቅጽል ስም ለማሳመን ወደ ኋላ አላሉም። ወልደጊዮርጊስ ይህን ሁሉ ሹመት ከተቀበሉ በኋላ፤ የሥልጣን ኃይላቸው እጅግ የናረና የዲክታተር ጠባይ የያዘ ነው በማለት የመሳፍንትና የመኳንንት ወገን ብቻ ሳይሆን፤ ከመንግሥት ባለሥልጣኖች መካከል ትልልቆቹም ሆኑ ትንንሾቹ፤ ከፍ ያለ ሥጋት አድሮባቸው በያለበት ሲወያዩ ይሰማ ነበር። የዚህ የጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ የሥልጣን አያያዝ ወደ ዲክታተርነት ሊያመራ ይችላል ብለን እንሠጋለን ከሚሉት መካከል፤ ከሀብተወልድ ቤተሰቦች አንዱ የሆኑት አቶ መክብብ ዳምጤ፤ ከአሳዳጊ አባታቸው ከአቶ መኰንን ጋር ግልጽ በሆነ መንፈስ በሰፊው የተነጋገሩትን ለዚህ መጽሐፍ ደራሲ በዝርዝር አጫውተውት ስለነበረ፤ የውይይታቸውን አካሄድ ከዚህ እንደሚከተለው ያቀርበዋል።

መክብብ - ወንድም ጌታ! እባክህ እኔ የተጨነቅኩበትን ጉዳይ ገልጬ እንድነግርህና አንተም የምታውቀውን ትክክለኛውን ነገር አድታስረዳኝ ልመናዬን ተቀበለኝ።

መኰንን - እኔ፤ አንተንና ወንድሞችህን አካለወርቅንና አክሊሉን ሳሳድጋችሁ፤ በአገር ሆነ በቤተሰብ የግል ጉዳይ እያንዳንዳችሁ የምታስቡትንና መረዳት የምትፈልጉትን እንድትጠይቁኝ. ተስማምተን እንደነበረ ታስታውሳለህ! ስለዚህ ዛሬ የተለየ ፈቃድ የምትለምንበት ምክንያት አልገባኝም።

መክብብ - አስቀድሜ ፈቃድ የጠየቅኩት፣ የምገልጸው ጉዳይ የከበደና ድፍረት የተመረኮዘ መስሎ ስለታየኝ ነው እንጂ የሰጠኸንን ዕድልና ነፃነት ዘንግቼው አይደለም።

መኰንን - የፈለግከውን ተናገር አዳምጥሃለሁ።

መክብብ - እኔ በዛሬው ሰዓት በጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ሥልጣን ከሚሠጉት ሰዎች አንዱ ነኝ። እንደ እኔም የሚያስቡት ሰዎች በጣም ብዙዎች ናቸው። እኔና እኔን በመሳሰሉት ወዳጆቼ አስተያየት፤ የጃንሆይ አሠራር በወረት ላይ የተመሠረተ ሆኖ ነው የምናየው። ለምሳሌም ያህል፤ ከጠላት በፊት ዋና ወዳጃቸውና አማካሪያቸው አንተ ነበርክ። በዚያን ጊዜ አቶ ወልደጊዮርጊስን ያስተዋወቅካቸው አንተ ስትሆን፤ ስለሰውየውም ትጋትና የሥራ ችሎታ በየጊዜው የሚያማክሩህና ለእድገታቸውም ሐሳብ

የምትሰጣቸው አንተ እንደነበርክ ሁላችንም እናውቃለን። ዛሬ ደግሞ የጃንሆይ አሠራር ተለውጦ፣ በሥልጣንም፣ በፕሮቶኮል አቀማመጥም ካንተ የሚቀድሙት ወልደጊዮርጊስ ሆነዋል። በጽሕፈት ሚኒስትርነታቸው ብቻ የንጉሠ ነገሥቱ አፈጉባኤ፣ የንጉሠ ነገሥቱ ዋና ማህተም ያዥ፣ የንጉሠ ነገሥቱ አዋጅ ነጋሪ ነኝ ብለው፣ ከእሳቸው በፊት የነበሩት ጸሐፊ ትዕዛዞች ሁሉ ያልነበራቸውን ሥልጣን አስፋፍተው ከመያዛቸው በላይ፣ በዛሬው ጊዜ ደግሞ የአገር አገዛዙን፣ የፀጥታውንና የፖሊስ ኃይሉን ጠቅልለው በመያዛቸው ተወዳዳሪ የሌላቸው ሆነዋል። እረ ለመሆኑ ይህ ሁሉ ለእናንተ ይታያችኋል ወይ? በእኛ በታናናሾቻችሁ አስተያየት፣ ወልደጊዮርጊስ ቁራጥና ፍጹም ዲክታተር በሆነው መንፈሳቸው ይህን ሁሉ ሥልጣን ይዘው ከቆዩ፣ እንኳንስ እናንተን ሚኒስትሮቹን ለማግለል ይቅርና፣ ሲመቻቸው ጃንሆይንም ከሥልጣን ለማውረድ እንደማይመለሱ ግልጽ ሆኖ ይታየናል። እኔ በዚህ ጉዳይ በጣም እሠጋለሁ። ወንድሜ አባቴ ከሆንከው ከአንተ ዘንድ ከመምጣቴ በፊት፣ ወንድሞቼን አካለወርቅንና አክሊሉን ይህንኑ ስሜቴን ገልጬ አጫውቻቸው ነበር። አካለወርቅ፣ " ... ቀጥታ በማይመለከትህ ጉዳይ አዕምሮህን ለምን እንደምታስጨንቅ አልገባኝም። ከዚህ ቀደም የማውቀውን ነግሬሃለሁ። ጸሐፊ ትዕዛዝ በየጊዜው አንተን ከሹመት የሚዘሉህ፣ ስለ እሳቸው በያለበት የምትሰጠውን አጉል ትችት እየሰሙ ነው። አንተ ዛሬ የምትጨነቅበትን ጉዳይ እንኳንስ ብቻህን ሆነህ፣ የሀብተወልድ ልጆች ሁላችንም ብንተባበርህ፣ የሚለወጥ ወይም የሚሻሻል ነገር አይኖርም ..... " አለኝ። አክሊሉ ደግሞ የባሰ ሆነብኝ። " .... ለመሆኑ አንተ ቀጥታ በማይመለከትህ ጉዳይ ገብተህ ብቻህን "ቫልስ" የምትደንሰው፣ ምን ለማስለወጥ ? ወይም ምን ለማሻሻል ነው? ..... " ብሎ ሳቀብኝ። ለአክሊሉ ደህና አድርጌ መልሼለታለሁ። አንተ እስከዚህ የምትቀልደው፣ በጸሐፊ ትዕዛዝ ዘንድ ተወዳጅና ተደናቂ ስለሆንክ፣ ምንም አይደርስብኝም ብለህ ነው። አይምሰልህ! ሲደርስ ታየዋለህ። አንተንና አንተን የመሳሰላችሁት፣ ከሚኒስትርነት ደረጃ ላይ የደረሳችሁት ወጣቶች ሁሉ፣ ስለ ዛሬውና ስለ ነገው የአገራችን አስተዳደር ጉዳይ በሕብረት ብታጠኑትና ብትነጋገሩበት፣ ወደፊት ከሚጠብቀን ከወልደጊዮርጊስ የዲክታተር መሪነት እኛንም እናንተንም ለማዳን ትችሉ ነበር። ግን፣ ምን ይሆናል? እኔ እንደማያችሁ፣ አደጋው እላያችሁ ላይ ሲወድቅ ካላያችሁት አትንቀሳቀሱም። .... አንተ ብቻህን ቫልስ ብትደንስ ምን ውጤት ታመጣለህ? ብለኸኛል። መጀመሪያ እኔ ቫልስ አልደንስም። በቫልስ መሽከርከሩን ለባለቤቱ ለአንተ እተውላለሁ። ስለ አገራችን አስተዳደር ጉዳይ ሐሳቤን የሚያዳምጠኝ እስከማጣ ድረስ መናገሬን አልተውም አልኩት። በዚህ ዓይነት ወንድሞቼ ተስፋ ለማስቆረጥ ቢሞክሩኝም፣ ተስፋዬን ሳልቆርጥ ወደ አንተ ወደ ወንድም አባቴ ዘንድ ተነሥቼ መጥቻለሁ። ስለ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ የሥልጣን ኃይል የተናገርኩትና የምሠጋው ስሕተት ነው? ወይስ ልክ ነው? መልሱን ስጠኝ !

መኮንን የተናገርካቸውን ሁሉ በሚገባ አድምጫለሁ። እኔም በተራዬ የምናገረውን ማድመጥ ያንተ ፋንታ ነው።

አንተ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስን በሩቅ ሆነህ የምትገምተው፣ እኛ በየቀኑ በቅርብ ከምናየው የተለየ ነው። ይህንንም ስል ትክክለኛውን ሁኔታ ማየት የሚችሉት በቅርብ ያሉት ብቻ ናቸው ለማለት አይደለም። አንዳንድ ጊዜ በቅርብ ላሉት ሰዎች የተሸፈነው ጉዳይ፣ በሩቅ ለሚያዩት የተሻለ ይገለጥላቸው ይሆናል። ስለዚህም፣ እኔ የምነግርህ የራሴን አመለካከት ብቻ ነው።

እኔ እንደሚመስለኝ፣ ለጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ የሚጠቅመው፣ ለጃንሆይና ለመንግሥታቸው እስካሁን ያሳየውን ታማኝነቱንና ጠንካራ ሠራተኛነቱን ሲቀጥል ነው እንጂ፣ ለኢትዮጵያ አስተዳደር የሥልጣን ባለቤት ለመሆን ሲከጅል አይደለም። እስከማውቀውም ድረስ፣ ጸሐፊ ትዕዛዝ ምንም ሥልጣኑን ማስፋፋት የሚወድ ቢሆንም፣ ጃንሆይን ለማግለል እስከዚህ የሚሳሳት አይመስለኝም። ምናልባት እንዳልከው፣ የጃንሆይ የቅርብ አማካሪዎች ናቸው የምንባለውን ሚኒስትሮች፣ ከቤተመንግሥቱ እንድንርቅ በማድረግ ብቻውን ባለሙሉ ሥልጣን ሆኖ መሥራትን ይመኝ ይሆናል። ይህንን ዕድል ደግሞ ጃንሆይ ምንጊዜም አይሰጡትም። የቅርብ ረዳቶቻቸውን እያራቁ፣ በጸሐፊ ትዕዛዝ ብቻ እየተመሩ የሥልጣን ባይተዋር ሆነው መኖርን የሚቀበሉ ሰው አይደሉም። በመሠረቱ፣ ሥልጣንን በመውደድ ከሁሉም የሚበልጡት ጃንሆይ ራሳቸው ናቸው።

እኔንና ጸሐፊ ትዕዛዝን የሚያስማማንና አንድነት እንድንሰለፍ ያደረገን፣ መጀመሪያ ሁለታችንም ለጃንሆይ ታማኝነታችንን ማጠንከርና እሳቸውም በእኛ ላይ ዕምነታቸውን እንዲያሳርፉ ማድረግ ሲሆን፣ ሁለተኛ ደግሞ ጃንሆይን ይዘን የአገራችንን አስተዳደር ከመሳፍንት አገዛዝ ለማላቀቅ አንድ ዓይነት ምኞት ያደረብን ሰዎች በመሆናችን ነው። ይህ ትናንት የገነባነው መንፈሳችን እስከ ዛሬ ንፋስ አልገባበትም። ነገርን ነገር ያነሣዋል እንደሚባለው፣ አንድ ምሥጢር ልንገርህ! እስከ ዛሬ ለወንድሞችህ አልነገርኳቸውም። ጃንሆይ፣ አማቻቸውን ቢትወደድ መኮንን እንዳልካቸውን ጠቅላይ ሚኒስትር ለማድረግ በወሰኑ ጊዜ፣ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስን የአገር ግዛት ሚኒስትር እንዲያደርጉት ሐሳቡን በቅድሚያ ያቀረብኩትና ደጋግሜም ያመለከትኩ እኔ ነኝ። ነገር ግን፣ የአገር ግዛት ሚኒስትርነትን ሲሰጡት፣ የጽሕፈት ሚኒስትርነቱን እንደያዘ ይሆናል ብዬ ጨርሶ አላሰብኩም። እንዲያውም፣ ለጽሕፈት ሚኒስትርነት ከሁለት ሰዎች መካከል አንዱን እንዲመርጡ አቅርቤላቸው፣ ጃንሆይም ተስማምተውበት ነበር። በመጨረሻው፣ ጃንሆይ ማንንም ሳያማክሩ፣ "ወልደጊዮርጊስ የጽሕፈትና የአገር ግዛት ሚኒስትር" ብለው ሹመቱን ሲጋባው ሳይሆን ራሳቸው ንጉሠ ነገሥቱ አወጁለት። ይህን ለምን ሲሉ

እንዳደረጉ አልገባኝም። እኔም ምክንያቱ ምን ኖርዋል? ብዬ አልጠየቅኋቸውም።

አሁን አንተና ወዳጆችህ የሠጋችሁት፤ እነዚህን ሁለት ሚኒስቴሮች አጣምሮ በመያዙ፤ ሥልጣኑ ወሰን አጥቶ እንኳንስ ለእኛ ለቅርብ አገልጋዮቻቸው፤ ለራሳቸውም ለጃንሆይ አደገኛ ይሆናል ብላችሁ ነው። ለእናንተ ይህ ሁሉ የታያችሁ፤ በሐሳባችሁ መስሎአችሁ ነው? ወይስ በግብር የሚታይ የተጨበጠ ነገር ይዛችሁ ነው? እኔ በበኩሌ፤ እንደዚህ አይታየኝም። ዛሬ ያለውን ሁኔታ የምናየው በዛሬው ዕለት ብቻ ስለሆነ፤ ነገና ተነገ ወዲያ የሚሆነውን በትክክል አናውቀውም። ስለዚህም፤ ነገ የሚሆነውን ጉዳይ ዛሬ እርግጠኛ ሆኜ መናገር አልችልም። ደግሞም ከዚህ በቀር ሥጋታችሁ ሁለት ሚኒስቴሮች ተደርበው ለምን ሰጡት? በማለት ከሆነ፤ እኔም ዛሬ የርሻ፣ የንግድና የኢንዱስትሪ ሚኒስትር ተብዬ ሁለቱን ሚኒስቴሮች በአንድነት ይዣለሁ። በዚህ አኳኋን፤ እኔንስ ለምን ወደ ዲክታተርነት ከሚያመሩት ባለሥልጣኖች ጋር አትቆጥሩኝም?

መኮብብ - ወንድም ጌታ! እንዳቋርጥህ ፍቀድልኝ። የእርሻ፣ የንግድና የኢንዱስትሪ ሚኒስቴሮች ሥልጣን፤ ከጽሕፈትና ከአገር ግዛት ሚኒስቴሮች ጋር የሚወዳደር አይደለም። የንጉሠ ነገሥቱን ዋና ማህተምና፤ የአገር አስተዳደሩን ሥልጣን ለአንድ ሰው ማሸከም፤ ሕዝቡን ቀጥቅጠህ ግዛ እንደ ማለት የሚቆጠር ነው። ጃንሆይ ያደረጉት ስሕተት እጅግ ከባድ ነው። በተጨማሪም፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ በያዙት ሥልጣን ምን ያህል እንደተመኩና ምን ያህል እንደተሰማቸው፤ መገመት የምንችለው፤ እኛ ትንንሾቹ ነን እንጂ እናንተ ትልልቆቹ አይደላችሁም።

መኮንን - አሁንም ደግመህ የነገርከኝ ስሜትህን ነው እንጂ፤ በጸሐፊ ትዕዛዝ የዲክታተር አሠራር ላይ የተጨበጠ ማስረጃ ይዘህ አይደለም። ምናልባት! እነዚህን ሁለቱን ሚኒስቴሮች ጸሐፊ ትዕዛዝ እንዲመራቸው መደረጉ ምን ችግር እንደፈጠረ ብገልጽልህ፤ ሥጋትህን ያሻሽልልህ ይሆናል። .....

..... በጃንሆይ ዘመነ መንግሥት፤ የጽሕፈትና የአገር ግዛት ሚኒስቴሮች ፍጹም የተለያዩ ተግባሮች ያሏቸው በመሆናቸው፤ በአንድ ሰው መመራት የሚችሉ አይደሉም። የጽሕፈት ሚኒስትር ማለት፤ ምንም እንኳን አንተ ሥልጣኑን ወይም ኃላፊነቱን ከሁሉም ሚኒስቴሮች በላይ አድርገህ ብታሳብጠው፤ ትክክለኛው ትርጉሙ የጃንሆይ ጸሐፊና የጽሕፈት ቤታቸው መሪ ማለት ነው። የጃንሆይ ጸሐፊ ደግሞ፤ ከጃንሆይ ምን ጊዜም መለየት የማይችል ሰው ነው። በዚህም ምክንያት፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ ቀኑን ሁሉ የሚያሳልፈው ከጃንሆይ ጋር ከሆነ፤ ያንን ትልቁን የአገር አገዛዙን ጉዳይ መቼ ሊሠራው ነው? እስካሁን ሁላችንም እንዳየነው፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ ከልቡ አስበበት የነበረውና እኛም የሥራ ጓደኞቹ ብዙ ተስፋ ያደረግንበት የአገር ግዛት ሚኒስቴር ጉዳይ የምንጠብቀውን ያህል

የመሻሻል ለውጥ አልተደረገበትም። ስለዚህ፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ የአገር አገዛዙን ጉዳይ ከጽሕፈት ሚኒስትርነቱ ጋር ደርቦ በመያዙ፤ የሥልጣኑ ኃይል ከልክ በላይ ሆኗል እየተባለ የሚወራው ሁሉ ውሸት መሆኑን እንድትረዳው እፈልጋለሁ። በዛሬው ሰዓት፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ በሥልጣን እንኳንስ ጃንሆይን ለማስቸገር፤ እኛንም ለማጥቃት የሚያስችል መንገድ የለውም። ....

ሁለተኛው ቅሬታህ፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ በፕሮቶኮል ከእኔ ቀዳሚ በመሆኑ ነው። ለዚህ አንድ ምሳሌ ብሰጥህ የሚበቃ ይመስለኛል። አንተና ወንድሞችህ በተማራችሁበት፤ እኔም በስደት በኖርኩበት በፈረንሣይ አገር፤ ያስተዋልኩት አንድ ነገር አለ። እንደምታውቀው የአገሩ አስተዳደር በዴሞክራሲ የተገነባ ነው እየተባለ በየዕለቱ ይጨበጨባል። ከዴሞክራሲውም ስፋት የተነሣ፤ በየወሩ መንግሥት እየፈረሰ አዲስ መንግሥት ይቋቋማል። እዚህ ላይ ልብ ብዬ ያስተዋልኩት፤ መንግሥት ፈርሶ አዲሱ መንግሥት ሲቋቋም፤ ያ ጠቅላይ ሚኒስትር ሆኖ የፈረሰውን መንግሥት ይመራ የነበረው ባለሥልጣን፤ በአዲሱ መንግሥት ውስጥ የውጭ ጉዳይ ወይም የኢኮኖሚ ሚኒስትር ተብሎ ሲሾም ይታያል። እንግዴህ፤ ጉዳዩን ግልጽ አድርጐ ለማሳየት፤ ያ በፊት አዛዥ የነበረው ሰው፤ አሁን ደግሞ በተራው ታዛዥ ይሆናል ማለት ነው። ይህን የመሰለው አሠራር እጅግ በሥልጣኔ በተራመዱት አገሮች የሚፈጸም ከሆነ፤ በእኛስ አገር እንዲሠራበት ቢደረግ ምን ነውር አለበት? ... ቅድም እንደጠቀስከው፤ ከጣልያን ጦርነት በፊት፤ እኔ ለብዙ ጊዜ ከበላዬ ሚኒስትር ሳይሾምብኝ በዋና ዲሬክተርነት የርሻና የሥራ ሚኒስቴርን፤ የንግድ ሚኒስቴርን እየመራሁ የሚኒስትሮች ምክር ቤት አባል ነበርኩ። በዚያን ጊዜ የፕሮቶኮል ደረጃዬ ከወዳጁ ከአቶ ወልደጊዮርጊስ በጣም የቀደመ እንደነበረ የታወቀ ነው። ፋሽስት ከተባረረ በኋላ፤ ወዲያው ጃንሆይ በገቡ በአሥረኛው ቀን፤ አቶ ወልደጊዮርጊስ ጸሐፊ ትዕዛዝ ተብሎ የጽሕፈት ሚኒስትር የሆነው፤ እኔ ከስደት ከመመለሴ በፊት ነበር። እኔ ከስደት አገሬ እንደገባሁ፤ ጃንሆይ አዘጋጅተው የጠበቁኝ የእርሻ ሚኒስትርነትን ሲሆን፤ በፕሮቶኮል ረገድ ወዳጄ ጸሐፊ ትዕዛዝ ከእኔ ቀድሞ የሚኒስትርነትን ሹመት አግኝቷል። ስለዚህ፤ የፕሮቶኮል ቅድሚያ የተሰጠው በትክክለኛው ሥርዓት መሆኑን ማመን አለብን። <u>ጸሐፊ ትዕዛዝ ግን፤ ወዳጄ መኮንን ሀብተወልድ በዕድሜም በአገልግሎትም ስለሚበልጠኝ፤ እኔ በፕሮቶኮል እሱን መቅደም አይገባኝም ብሎ፤ ከእልፍኝ አስከልካዩ ከሻለቃ መርዕድ መንገሻ (ኋላ ሌ.ጄኔራል)</u> ጋር በሰፊው መከራከሩን ሰምቻለሁ። ይህም የሚያሳየው ጸሐፊ ትዕዛዝ ለእኔ ያለውን አክብሮትና ቅን መንፈስ ነው።

በተጨማሪም፤ እኔ በአሁኑ ሰዓት በጸሐፊ ትዕዛዝ ላይ ያለኝ መልካም አስተያየት እስከምን ድረስ እንደሆነ እንድትረዳው፤ ከልቤ የማስበውን ምኞቴን ልገልጥልህ እወዳለሁ። አንድ ቀን ጃንሆይ፤ ለቢትወደድ መኰንን እንዳልካቸው ሌላ ሥራ ፈልገው ጸሐፊ ትዕዛዝን ጠቅላይ ሚኒስትር ቢያደርጉት፤ ከማንም የበለጠ

የምደሰት መሆኔን አረጋግጥልሀለሁ። ደስታዬም፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ ከድሃው አብራክ የመጣ ወገኔ ነው በማለት ብቻ ሳይሆን፤ በችሎታውና በሠራተኛነቱ ስለምተማመን ነው። እርግጥ ነው! ይህ ምኞት እንደታሰበው ሊሰምር የሚችለው፤ ዛሬ ያሉት ሁኔታዎች ሁሉ ምንም ዓይነት እንከን ሳይገጥማቸው በትክክል የሚቀጥሉ ከሆኑ ነው። ይህም ማለት አንደኛው፤ በጃንሆይና በጸሐፊ ትዕዛዝ መካከል ያለው መተማመን እያማረበት ከቀጠለ ሲሆን፤ ሁለተኛው ደግሞ፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ ከእኛ ከሥራ ጓደኞቹ ጋር እስከ ዛሬ ያሳየውን መግባባትንና ሕብረትን በይበልጥ እያጠነከረ ከተጓዘ ነው። አለበለዚያ፤ እናንተ ወጣቶቹ እንደሚታያችሁ፤ የጸሐፊ ትዕዛዝ የሥልጣን አጠቃቀም ወደ ዲክታተርነት አምርቶ፤ በጃንሆይና በአስተዳደራቸው ላይ ችግር የሚፈጥር ከሆነ፤ በመሪነቱ ብዙ ሳይቆይ ባጭሩ ሊቀጭ ይችላል። እንግዲህ፤ እንደምታየው ስለ ጸሐፊ ትዕዛዝ ያለኝ አስተያየት ከፍተኛ ነው። ቀደም ብዬ እንደአስጠነቀቅኩህ፤ ይህን አስተያየቴን የምሰጠው ዛሬ በአለው ሁኔታ ላይ ብቻ ተመሥርቼ ነው። ነገ ለሚደርሰው ጉዳይ ዛሬ ዋስትናት አልጠየቅም። ማናቸውንም የምወስነው እንደ አመጣጡ አይቼ ነው።

አሁን አንተን ወደሚመለከተው ጉዳይ ልመለስና፤ ወንድሞችህን አካለወርቅንና አክሊሉን ባማከርካቸው ጊዜ፤ አንዱ በጥሞና አንዱ በፌዝ ቢመልሱልህም፤ ከተናገሯቸው ቃላቶች ውስጥ በመጠኑ የሚለቀም ፍሬ ነገር አልጠፋም። በተለይ አካለወርቅ፤ በጽሕፈት ሚኒስቴር ዋና ዲሬክተርነቱ የጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ የቅርብ ረዳት ሆኖ ብዙ ነገሮችን የሚያውቅ ስለሆነ፤ የሚናገረውን ማቃለል አይገባም። አንተ፤ እስከዛሬ ድረስ በሹመት ከአንዳንድ ጓደኞችህ ያነስከው፤ በዕውቀት ማጠር ወይም በስንፍና ሳይሆን፤ ስለ ጃንሆይ አመራርና ስለ ጸሐፊ ትዕዛዝ ሥልጣን የምትሰጠው የነቀፌታ ትችት እየተሰማብህ ነው። አካለወርቅም የነገረህ፤ ፍሬ ለማይሰጥ ነገር ለምን ራስህን ትጐዳለህ? ሲሆን፤ አክሊሉ ደግሞ የደረበልህ፤ ያንተ ብቻህን መፍጨርጨር ምን ለውጥ ያመጣል? ብሎ ነው። እኔ ደግሞ ዛሬ የምጨምርልህ፤ ይህንን በጃንሆይና በጸሐፊ ትዕዛዝ ላይ የምታሰማውን ነቀፌታ እርግፍ አድርገህ መተው አለብህ ብዬ ነው። አየህ? መክብብ! ይህን የመሰለውን ትልቅ ጉዳይ የምትጫዋወተው ከነማን ጋር መሆኑን በጥልቅ ብታስብበት ይሻላል። እኔ እንደምሰማው ወዳጆቼ የምትላቸው፤ እነ ዳኛ ገብረመድህን ጉሣ፤ ሲም ስሎሞን፤ ዘውድነህ ቅጣው፤ እና ሌሎቹም በዕውቀትም በሥልጣኔም ከሁሉም እንበልጣለን ብለው ራሳቸውን ከሚገባ በላይ እየካቡ፤ ሰውን ሁሉ ንቀው ብቻቸውን የሚንቀባረሩ ናቸው። ሱፍ ልብስ መቀያየር፤ ጋያ ማጨስ፤ መደቅሳ መጠጣት፤ ዳንስ መደነስ እና ወግ ሲያርቁ መዋል የትምህርትና የሥልጣኔ ምስክር ነው ብዬ አላምንም። እነዚህ ያንተ ወዳጆች እኛን እንደሚንቁሩን ሁሉ፤ እኛም ሥዕላቸው የሚታየን በዚህ በተናገርኩት መልክ ነው። ይኸውልህ ! እነዚህ ወዳጆችህ ናቸው፤ አንተ የምታጫውታቸውን ሁሉ እያፋፋሙ ለሌሎች በማስተላለፍ፤ በጃንሆይና በጸሐፊ ትዕዛዝ

ዘንድ ቂም ያስያዙብህ። ሁላችንም ደህና አድርገን እናውቅሃለን። አንተ የምታስበውን ሁሉ እንደልብህ አውጥተህ የምትናገር ነህ እንጂ፤ ተንኮል አዘጋጅ አይደለህም። ሆኖም ይህንን ጠባይህንና የልብህን ገርነት ለጃንሆይ ማስረዳቱ ቀላል አልሆነልኝም። በቅርቡ ስለ አንተ ሥራ ጉዳይ አንስቼባቸው፤ ገና ሐሳቤን ተናግሬ ሳልጨርስ፤ " ... **መኮንን እኮ ፈረንሣይ አገር የተማረው የራዲዮ ኢንጂኒየርነት ሳይሆን፤ በራዲዮ ሬሾሉሲዮን እንዴት እንደሚሠራጭ ነው** .... " አሉኝ። ጃንሆይ ይህን የተናገሩት እንደ ቀልድ ቢሆንም፤ እውነተኛውን ስሜታቸውን ያመለክታል። ስለዚህ፤ እኔ ደግሜ ደጋግሜ የምመክርህ፤ ጃንሆይን እንደ ወረተኛ፤ ጸሐፊ ትዕዛዝን እንደ ክፉ ሸረኛ፤ እያስመሰልክ የምትሰጠውን ትችት እንድታቆም ነው። ለአንድ ሰሞን ከየሰዉ ጋር መገናኘቱንና ሐሳብ መለዋወጡን ብታቆመው፤ በሥራህ ላይ ምን ውጤት እንደሚያስገኝልህ ታየዋለህ። ከዚህ ሌላ የምጨምረው የለም።

መኮንን - ወንድም ጌታ! በዝርዝር የገለጽክልኝን ሐሳብና የሰጠኸኝን ምክር ደህና አድርጌ ለመከተል እፈልጋለሁ። አንተ አባቴ ወንድሜ የነገርከኝ፤ በትክክል የምታውቀውንና የምታምንበትን ስለሆነ፤ እኔ በሩቅ ሆኜ ከምሰማውና ከሚታየኝ ልዩነቱ ብዙ ነው። ያለ ጥርጥር የኔ ጉድለት ነገ ሊደርስ ይችላል ብዬ የማልመውን ዛሬ ደርሶ እንደሚታይ በማስመሰል፤ አዕምሮዬን ማስጨነቄና ሥጋቴንም ለሰው ሳስረዳ ከሚገባ በላይ እያባባስኩ መናገሬ ይሆናል። አባቴ ወንድሜ ያስረዳኸኝም፤ በዛሬው ዕለት ያለውን ሁኔታ ነው እንጂ ነገ ለሚፈጠረው ወይም ለሚለዋወጠው ነገር መተንበይና ፍርድ ማስቀደም አልፈልግም ብለኸኛል። ሆኖም፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ዛሬ በአሉበት ሁኔታ ለጃንሆይና ለመንግሥታቸው አሥጊ አለመሆናቸውን ካረጋገጥክልኝ በኋላ፤ ለወደፊቱም ቢሆን የተጣለባቸውን ዕምነት እንድለው፤ በአስተዳደሩ ሥልጣን ላይ አምባገነን ለመሆን ቢሞክሩ፤ ጉዳት ላይ ከመውደቅ በስተቀር አንዳች ውጤት እንደማይኖራቸው፤ ተስፋ የሚያሳድር አስተያየት ሰጥተኸኛል። እንደዚህ ቢሆን ጥሩ ነበር። ነገር ግን፤ እኔ ጥርጣሬ የሚያድርብኝ፤ አጅሬ ዕድል ካገኙ፤ የአገሩን አስተዳደር ሥልጣን ጠቅልሎ ለመያዝ ለአንዲት ደቂቃ የሚያመነቱ ስላልሆኑ፤ የሚያስቡት ይሳካላቸዋል ብዬ ነው። በተለይ አንተ በቅንነት እንደምታስበው፤ አንድ ቀን ጃንሆይ ቆርጠው ጠቅላይ ሚኒስትር ቢያደርጓቸው፤ ያ የሚነገርላቸውን ጠንካራ ሠራተኛነትና ብልህነት ለዲክታተርነት አመራራቸው እንደሚጠቀሙበት እርግጠኛ ነኝ። ስለዚህ፤ አባቴ ወንድሜን የማሳስብህ ወልደጊዮርጊስን ለጠቅላይ ሚኒስትርነት ማጨት ተገቢ የሆነ ምርጫ አለመሆኑን ነው። እኔ ይህንን ስናገር፤ በሰውየው ላይ ጥላቻ ወይም የግል ቂም ያደረብኝ መስሎ ይታይብኝ ይሆናል። እኔ እሳቸውን የማልደግፈው፤ በሥልጣን አሠራራቸውንና ወገን መራጭ መሆናቸውን ነው። እሳቸው ግን እኔን እንደሚጠሉኝ በግልጽ እንዳውቀው አድርገዋል። ስለዚህ፤ በዘመነ ወልደጊዮርጊስ መኮንን ዳምጤ አንዳች ዕድገት

እንደማይታሰብለት ያውቀዋል። ደግነቱ መኮንን ልጅህ ወንድምህ፣ ለሹመት አይጓጓም። ለሀብትም አይሳሳም። በአባትነትህ የሰጠኸኝን ምክር ለመከተል እጥራለሁ። ሆኖም በጸሐፊ ትዕዛዝ ላይ ያለኝ አመለካከት ሙሉ በሙሉ የማይለወጥ መሆኑን ስገልጽልህ እንደማትቆጣኝ ተስፋ አደርጋለሁ።

ከዚህ በላይ እንደታየው፣ በዚያን ዘመን የወጣቱ የመኮንን ዳምጤና የመሰሎቻቸው አስተያየት ያተኮረው፣ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ በጽሕፈትና በአገር ግዛት ሚኒስትርነታቸው የያዙትን ሥልጣን እያስፋፉ ከተጓዙ፣ በመጨረሻው ቀዳማዊ ኃይለሥላሴን ከሥልጣን አግልለው አገሪቱን በዲክታተርነት ከመምራት አይመለሱም በሚል ሥጋት ነው። ነገር ግን፣ መኮንን ሀብተወልድ ይህ ዓይነቱ አስተሳሰብ ትክክል ነው ብለው አልተቀበሉትም። ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስም ምኞታቸው ከመስመር አልፎ እስከዚህ ድረስ እንደማይሳሳቱ ለማስረዳት ጥረት ቢያደርጉም፣ መኮንን ዳምጤ ሥጋታቸውን ሙሉ በሙሉ ሳያስወግዱ ተለያዩ።

የጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ሥልጣን ጉዳይ ይህን በመሳሰለው የሥጋት መንፈስ በያለበት ውይይት ሲደረግበት ከኖረ በኋላ፣ በኢት. አቆ. ሰኔ 30 ቀን 1941 ዓ.ም ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ባደረጉት ያልተጠበቀ ከፍተኛ የካቢኔ ሚኒስትሮች ለውጥ ውስጥ ፣

- የጦር ሚኒስትር የነበሩት ራስ አበበ አረጋይ የአገር ግዛት ሚኒስትር፣
- የጽሕፈትና የአገር ግዛት ሚኒስትር ሆነው ለስድስት ዓመታት የመሩት ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ፣ የጽሕፈትና የፍርድ ሚኒስትር፣
- የርሻ የንግድና የኢንዱስትሪ ሚኒስትር ሆነው ለስድስት ዓመታት የሠሩት አቶ መኮንን ሀብተወልድ የገንዘብ ሚኒስትር፣

ሆነው መሾማቸውን የሚያበሥረው አዋጅ ሲነገር፣ ከእንግዲህ ወዲህ የወልደጊዮርጊስ ሥልጣን ተዳከመ በማለት፣ ተቃዋሚዎች በሆኑት በአብዛኛዎቹ አገረ ገዥዎችና በአንዳንድ ሚኒስትሮች እንዲሁም የጦርና የሲቪል ሹማምንቶች በሆኑት ዘንድ ከፍ ያለ ደስታ ተፈጠረ። ይህም ደስታ የተፈጠረው፣ ወልደጊዮርጊስ በሥልጣን ከሚያተራምሱበት ከአገር ግዛት ሚኒስትርነት ከተሻሩ፣ ሌላ ምን የሥልጣን ኃይል ሊኖራቸው ይችላል? በሚል አስተሳሰብ ነበር። ይህ ሁሉ ከተቃዋሚዎቹ የተሰጠው ስሜታዊ አስተያየት፣ የምኞት መግለጫ እንጂ፣ እውነት ሆኖ የሚታይ አልነበረም። አንዳንዶቹም፣ የወልደጊዮርጊስን ከአገር ግዛት መነሣት እንደ ሽረት በመቁጠር ቢደሰቱበትም፣ የዋናው ወዳጃቸው የመኮንን ሀብተወልድ የገንዘብ ሚኒስትርነት ትልቅ ሥልጣን ስለሆነ፣ በጀቱንና ገንዘቡን የሚያዙበት እነሱ ሁለቱ ናቸው በማለት፣ ቅሬታቸውን ከመግለጽ አልተቆጠቡም ነበር።

ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ፣ ለስድስት ዓመታት የኖሩበትን የአገር ግዛት ሚኒስቴርን ለራስ አበበ አረጋይ ሲያስረክቡ፣ በሚኒስቴሩ ዋና ዋና የሥራ ዘርፎች ላይ የመደቧቸው ባለሥልጣኖች፣ በተለይም ለፀጥታው (ሴኩሪቲ) ከፍተኛ ኃላፊዎች የሆኑት ምክትል ሚኒስትሩ ኮሎኔል ክፍሌ ዕርገቱና ዋና ዲሬክተሩ አቶ አልፍሬድ ሻፊ፣ ለወልደጊዮርጊስ ታማኝነታቸውን ለመቀጠል የተዘጋጁ ናቸው። አዲሱ ሚኒስትር ራስ አበበም በኢትዮጵያ ሕዝብ ዘንድ በጀግንነትና በትክክለኛ ፍርድ



ክቡር አቶ መኰንን ሀብተወልድ

" ... አንድ ቀን ጃንሆይ ለቢትወደድ መኰንን እንዳልካቸው ሌላ ሥራ ፈልገው ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስን ጠቅላይ ሚኒስትር ቢያደርጉት፤ ከማንም የበለጠ የምደሰት መሆኔን አረጋግጥልሃለሁ ... "

(መ.ሀ.ወ)

" ... አንተ በቅንነት እንደምታስበው፤ አንድ ቀን ጃንሆይ ቆርጠው ጸሐፊ ትዕዛዝን ጠቅላይ ሚኒስትር ቢያደርጓቸው፤ ንጉሠ ነገሥቱን ዘወር አድርገው አገሩን የሚመሩት እሳቸው ብቻ እንደሚሆኑ እርግጠኛ ነኝ ... "

(መክብብ)



አቶ መክብብ ዳምጤ

አሰጣጥ እጅግ የተከበሩና የተደነቁ ቢሆኑም፣ ፀጥታን በሚመለከት ጉዳይ እንደ ወልደጊዮርጊስ አንጀት ጉበት እያወጡ የመከታተል ዝንባሌ የላቸውም። ስለዚህ፣ አጅሬ ወልደጊዮርጊስ ምንም በኦፊሲየል የአገር ግዛት ሚስቴርን ቢለቁም፣ ባለሥልጣኖችን ለመከታተል የሚያስችላቸውን መሣሪያ በያለበት በመዘርጋታቸው፣ ከእጃቸው የሚያመልጥ ነገር አልነበረም።

የንጉሠ ነገሥቱ የቅርብ አገልጋዮች የሆኑት አንዳንድ ታላላቅ ሰዎች እንደገለጹት፣ ጃንሆይ ወልደጊዮርጊስን ከአገር ግዛት ያነሷቸው፣ ከየጠቅላይ ገዥዎች የሚደርሳቸው ስሞታ ስለበዛባቸው ነው እንጂ፣ በሰውየው ጠንካራ ሠራተኛነት እንከን አግኝተውባቸው አይደለም ። " ..... ምንነው? ጃንሆይ እርስዎ እያሉልን፣ እንዴት እንደተራ ሰው ውርደትና መንገላታት ይደርስብናል? .... ሠርተን እንዳልሠራን፣ ደክመን እንዳልደከምን፣ ምንም አልሠራችሁም እየተባልን በየዕለቱ በማዘዣ የሚደርስብን ወቀሳ እጅግ አስመርሮናል። ጃንሆይ፣ በተሰቀለው አምላክ፣ ደሙ በፈሰሰው ከዚህ አለቃ ይገላግሉን .... " በሚል ቃል ከየገዥዎቹ የሚደርሷቸውን ስሞታዎች፣ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ለተወሰነ ጊዜ ቢታገሡም፣ በመጨረሻው ሰላም ለማግኘት፣ ወልደጊዮርጊስን ከማንሣት በስተቀር ሌላ መንገድ አላገኙም። በዚህ አኳኋን ሹም ሽሩ ከተደረገ በኋላ፣ አገረ ገዥዎቹ ራስ አበበን በማግኘታቸው ለደስታቸው ወሰን አልሰጡትም ነበር። አበበ አረጋይ፣ በተፈጥሮ ካላቸው ትዕግሥትና ቅንነት ጋር ትልቁንም ትንሹንም ጌታዬ ነህ ! ወንድሜ ነህ ! እያሉ በማንከባከብ ስለሚያነጋግሩና እያንዳንዱንም ባለ ጉዳይ በእርጋታ እያዳመጡ የፍርድ በደል እንዳይደርስ የሚጥሩ አዋቂ ሰው በመሆናቸው፣ የአገር ግዛት ሚኒስትርነታቸውን በደስታ የተቀበለው፣ የሁሉም ወገን ነው።

ከዚህ በፊት እንደተገለጸው፣ ጸሐፊ ትዕዛዝ አገር ግዛትን ሲለቁ፣ ከእንግዲህ ወዲህ የሚኖራቸው ሥልጣን ያው የፊተኛው የጽሕፈት ሚኒስትርነቱ ካልሆነ በስተቀር፣ በጠቅላላው በንጉሠ ነገሥቱ መንግሥት ላይ የነበራቸው ተደማጭነት ይዳከማል ተብሎ እንደተገመተ ይታወሳል። የዚህም ዓይነቱ አስተያየት በአገር ውስጥ ብቻ ሳይሆን፣ በውጭ አገሮችም መንግሥታት ዘንድ ሲውጠነጠን የሰነበተ ነበር። ስለዚሁ ጉዳይ፣ በኢትዮጵያ የፈረንሣይ አምባሳደር የነበረው ሙሴ ሐንሪ ሩ. ለአገሩ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር በላከው ራፖር የገለጸውን መመልከት ተጨማሪ መረጃ ይሆናል። " .... ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ በቅርቡ ከፍተኛውን የካቢኔ ለውጥ ካደረጉ በኋላ፣ ከአገር ግዛት ወደ ፍርድ ሚኒስትርነት የተዛወረው ኃይለኛው ባለሥልጣን ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ፣ እቢሮው ጠርቶኝ ያቀረበልኝ ጥያቄ፣ " .... በአውሮፓ ዋና ዋና አገሮችና በተለይም በፈረንሣይ፣ የአገሩ መሪ ሹፍ ደ-ካቢኔ አድርጉ የሚሾመው ሰው፣ ሥልጣኑ እስከ ምን ድረስ ነው? .... " የሚል ነበር። እኔም በሰጠሁት መልስ፣ የሹፍ ደ-ካቢኔ ተግባር፣ እንደየአገሩ መሪ ሥልጣን የሚለያይ ነው። ለምሳሌ፣ በአገሬ በፈረንሣይ፣ የመንግሥቱ መሪ ጠቅላይ ሚኒስትሩ ስለሆነ፣ እሱ የሚሾመው ሹፍ ደ-ካቢኔ፣ የየሚኒስቴሮቹን ሥራ የሚያስተባብርና የጠቅላይ ሚኒስትሩን መመሪያ የሚያስተላልፍ በመሆኑ፣ የተከበረና ከፍተኛ ኃላፊነት ያለው ነው ብዬ አስረድቼዋለሁ። ወልደጊዮርጊስ ይህን ጥያቄ ያቀረበልኝ፣ ምናልባት ለንጉሠ ነገሥቱ ጽሕፈት ቤት፣ እስከ ዛሬ ያልነበረውን የሹፍ ደ-ካቢኔ ቢሮ ለማቋቋም ታስቦ ይሆናል ብዬ ጠረጠርኩ። የጠረጠርኩት ልክ ሆኖ ከተገኘም፣ የጽሕፈት ሚኒስቴር የተባለውን መሥሪያ ቤት መሰረዝ የሚያስፈልግ ይመስለኛል ሲል የፈረንሣይ አምባሳደር ራፖሩን ደምድሟል። የፈረንሣይ አምባሳደር እንዳለው፣ ጸሐፊ ትዕዛዝ፣ አገር ግዛትን በለቀቁ ማግሥት፣ የጽሕፈት ሚኒስትርን ተግባርና ኃላፊነት እጅግ ከፍ በማድረግ፣

በንጉሠ ነገሥቱ ስም የመንግሥቱን ጠቅላላ ሥራ ለመቆጣጠርና ለማስተባበር ፈልገዋል ማለት ነው። ይህም እውነት መሆኑን የሚያስረዳን፣ ከወልደጊዮርጊስ ዋና ዋና ወዳጆች መካከል አንዱ የነበሩት ብ.ጄኔራል መኮንን ደነቀ፣ በዚያን ጊዜ የግርማዊነታቸው ዋና የእልፍኝ አስከልካይ ከብዙ ዓመታት በኋላ ያጫወቱኝን ስንመለከት ነው። " .... ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ከአገር ግዛት ተነሥተው ምንም ዓይነት ድርጅት ወደሌለበት ወደ ፍርድ ሚኒስቴር ሲዛወሩ፣ ለሁላችንም ከእንግዲህ ወዲህ የአጅሬ ሥልጣን የአከተመ መስሎን ነበር። ይህ ሹመት እንደተደረገ ቀኑን በትክክል ባላስታውሰውም፣ አንድ ጠዋት ጃንሆይና ጸሐፊ ትዕዛዝ ብቻቸውን በአምሳለ ገነት ጽሕፈት ቤት ከሦስት ሰዓት ያላነሰ ጊዜ የቆይታ ንግግር አደረጉ። እኛም እውጭ ቆመን ይህን ያህል የቆይታ ንግግር የሚደረገው በአገር ላይ ምን ችግር ቢደርስ ነው! እያልን ስናወጣና ስናወርድ፣ የችሎት ሰዓት ደርሶ ጃንሆይ ከቢሮአቸው ሲወጡ፣ በጸሐፊ ትዕዛዝ ገጽታ ላይ የሚታየው ፈገግታ አገር ሰላም መሆኑን ለማመን አስቻለን። ከዚያም ሊጋባው ጃንሆይን እየመራ ወደ ችሎቱ ስገነት ሲወስዳቸው፣ እኔ እጥፍ ብዬ ወደ ጸሐፊ ትዕዛዝ በመሄድ፣ ምነው ምን ደረሰ? ብዬ ጠየቅኋቸው። ወዳጃቸው በመሆኔ ስለሚያምኑኝ፣ በቆይታ የተደረገው ንግግር ምን እንደነበረ አልደበቁኝም። " .... የጽሕፈት ሚኒስትርን ተግባርና ኃላፊነት አንድ ዓይነት መልክ ለመስጠት ከጃንሆይ ጋር በረዥሙ ተነጋግሬ አስወሰኛለሁ። እስከ ዛሬ ስንሠራበት እንደቆየነው፣ የጽሕፈት ሚኒስትሩ ተግባር የንጉሥ ቀላጤ እየሆነ ትዕዛዝ ማስተላለፍ ብቻ ሳይሆን፣ ከንጉሠ ነገሥቱ በተሰጠው መምሪያና ውሳኔ መሠረት፣ እያንዳንዱ ሚኒስትር ሥራውን በትክክል መፈጸም አለመፈጸሙን በመቆጣጠር ሥልጣን እንዲኖረው፣ ጃንሆይ ተስማምተውልኝ ደስ ብሎኛል .... " አሉኝ። እውነትም ከዚህ ጊዜ ጀምሮ ለጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ከፍተኛ ክብርና ሥልጣን መስጠቱን ተረዳሁ። ቀድሞ ጃንሆይ ቢሮ ቁጭ ብለው እንዲነጋገሩ ወንበር የሚዘጋጅላቸው፣ ለራስ ካሣና ለአቡኑ ብቻ ነበር። ከጥቂት ጊዜ ወዲህ ደግሞ ሁልጊዜም ባይሆን አልፎ አልፎ ለራስ አበበ አረጋይና ለቢትወደድ መኰንን እንዳልካቸው ወንበር ሲታዘዝላቸው አይቻለሁ። አሁን ግን ከአቶ መኰንን ሀብተወልድ በስተቀር፣* ሌሎቹ ሚኒስትሮች በየተራ በእቃቤ ሰዓት ጃንሆይ ቢሮ በሚገቡበት ጊዜ፣ ለጽሕፈት ሚኒስትሩ ወንበር ይሰጣቸውና ቁጭ ሲሉ፣ የጽሕፈት ሚኒስቴር ዋና ዲሬክተር ቆሞ ማስታወሻውን እንዲይዝ ተደረገ።

..... አንድ ሚኒስትር በተመደበለት "ዓቃቤ ሰዓት" ከንጉሠ ነገሥቱ ዙፋን ቀርቦ፣ ስለሚመራው ሚኒስቴር እስካሁን ያከናወነውንና ወደፊትም ለመሥራት

ያቀደውን ሲያቀርብ፣ ከጃንሆይ በፊት አስተያየታቸውን በመስጠት የንጉሠ ነገሥቱን ውሳኔ የሚያዘጋጁት የጽሕፈት ሚኒስትሩ ሆኑ። ጃንሆይም ከጸሐፊ ትዕዛዝ የቀረበውን ሐሳብ ካዳመጡ በኋላ፣ መልካም ድጋፍ ለተሰጠው ሚኒስትር፣ " .... ወልደጊዮርጊስ የተናገርከው እኛ ከምናስበው ጋር የተገጣጠመ ሆኖ ስለአገኘነው፣ ሚኒስትራችን የጠየቀውን ፈቅደንለታል .... " ይላሉ። ወይም ደግሞ ሚኒስትሩ ሠራሁ የሚለውና ወደፊት እንድሠራ ይፈቀድልኝ ብሎ ያቀረበው ሐሳብ፣ በሚገባ ያልተብራራ ነው ተብሎ አስተያየት ከተሰጠበት፣ " .... ወልደጊዮርጊስ እንደተናገርከው፣ ያልተሠራውን ሠርቻለሁ እያሉ መደለልና፣

---

* ከጥንት ጀምሮ መኰንን ሀብተወልድ ከጃንሆይ ጋር የሚነጋገሩት ዓቃቤ ሰዓት፣ ከሌሎቹ ሚኒስትሮች የተለየ ነበር። ይኸውም፣ ከምሽቱ 1 ሰዓት እስከ 2 ሰዓት

ወደፊትም እሠራለሁ እየተባለ ሐሳብን በሽንበቆ መሠረት ላይ መገንባት፤ ታላቅ ጉዳት የሚያስከትል ስለሆነ፤ የሠራኸውንም ሆነ ወደፊት ለመሥራት የምታስበውን እየለየህ በጥልቀት አጥናው ..... " የሚል ወቀሳ ያወርዱበታል። በዚህ አኳኋን፤ መልካም ድጋፍ በማግኘት መልካም ውሳኔ የተሰጣቸው ሚኒስትሮች ሲደሰቱ፤ የወልደጊዮርጊስን ቡራኬ ባለማግኘታቸው፤ "ሥራህን በሚገባ አታውቀውም" እየተባሉ የተገሠፁት ሚኒስትሮች ደግሞ፤ ጸሐፊ ትዕዛዝን እያማረሩ ወደየቢሮአቸው ይመለሱ ነበር ሲሉ፤ ዋና የእልፍኝ አስከልካይ የነበሩት ጄኔራል መኰንን ደነቀ በሰፊው አጫውተውኛል።

ታሪክን ወደ ኋላ መለስ ብለን ስናጠና፤ በአፄ ምኒልክ ዘመነ መንግሥት በተጀመረው የአሠራር ሥርዓት፤ አንድ ሚኒስትር በዓቃቤ ሰዓት ቀርቦ ስለፈጸመው ተግባርና ስለወደፊቱ ሥራው ሲያስረዳ፤ ጸሐፊ ትዕዛዙ ተገኝቶ በማስታወሻ ቃል መቀበልና በመጨረሻም የንጉሠ ነገሥቱን ውሳኔ በማዘገየ ማስታወቅ እንጂ፤ ካልተጠየቀ በስተቀር፤ ጣልቃ ገብቶ ለንጉሠ ነገሥቱ አስተያየትና የውሳኔ ሐሳብ አያቀርብም ነበር። ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስም ከጣልያን ጦርነት በኋላ በግንቦት 7 ቀን 1933 ዓ.ም (15/05/1941) የጽሕፈት ሚኒስትር ሲሆኑ፤ ከእሳቸው በፊት እንደነበሩት እንደ እነ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደመስቀል ታሪኩና እንደ እነ ጸሐፊ ትዕዛዝ ኃይሌ ወልደሩፋኤል፤ በምኒልክ ዘመን የተጀመረውን ሥርዓት በመከተል፤ በዓቃቤ ሰዓት ላይ የንጉሠ ነገሥቱን ቃል ከመቀበል በስተቀር፤ ሚኒስትሩ ባቀረበው ጉዳይ ላይ የራሳቸውን አስተያየት ሲሰጡ አልታዩም። በዚያን ጊዜ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስን የማይወዱ ሚኒስትሮች፤ እንደ ደጃዝማች መኰንን እንዳልካቸው (ኋላ ቢትወደድ) የአገር ግዛት ሚኒስትር፤ እንደ ነጋድራስ ገብረ እግዚአብሔር ደስታ የንግድ የኢንዱስትሪና የሥራ ሚኒስትር፣ እንደ አቶ መኰንን ደስታ (ኋላ ደጃዝማች) የትምህርትና የሥነ ጥበብ ሚኒስትር፣ በአቃቤ ሰዓታቸው ከጃንሆይ ጋር በሚነጋገሩበት ጊዜ፤ ጸሐፊ ትዕዛዙ ጣልቃ ገብተው አስተያየት እንዳይሰጡ ይታገሉ እንደነበረ ታውቋል። ይህ ሁኔታ ለብዙ ዘመን አልቆየም። እጅሬ ቀስ በቀስ የሚፈልጉትን ከማድረግ አልታገዱም። አሁንም የአገር ግዛት ሚኒስትርነትን ሲለቁ፤ ተቃዋሚዎቻቸው እንደአሰቡትና እንደተመኙት፤ ሥልጣናቸው ወደ ቁልቁለት አቅጣጫ አላዘነበለም። በጥቂት ጊዜያት ውስጥ፤ የጽሕፈት ሚኒስቴርን ሥራና ኃላፊነት፤ እንደ ጠቅላይ ሚኒስትር ተግባር አስመስለው በማሳደግ፤ የትናንቱ ባለሥልጣን ወልደጊዮርጊስ፤ ዛሬም የበለጠ ባለሙሉ ሥልጣን ሆነው ብቅ አሉ። **እንግዲህ፤ ወልደጊዮርጊስ ኃይላቸው ተዳክሟል፤ ሥልጣናቸው አዘቅዝቋል ! ብሎ እጅ አንሳሡንና አክብሮቱን የቀነሰ፤ ሐሜታውንና ትችቱን በያለበት መንዛት የጀመረ ሁሉ ምን ይበጀው ይሆን? ያለው አማራጭ በቶሎ መንገዱን ቀልብሶ እነበረበት ቦታ መመለስና ለእጅሬ መስገድ ብቻ ነው።**

# ምዕራፍ ፲

# የመኰንን ሀብተወልድ ሥልጣንና አሠራር ጠባይ

በዚህ መጽሐፍ ክፍል 7 ምዕራፍ 1 ላይ የመኰንን ሀብተወልድ የሕይወት ታሪክ እንደተገለጸው፤ በሥራ ዓለም፤ ደረጃ በደረጃ እያደጉ በቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ዘመነ መንግሥት ከሙሉ ሥልጣን ጋር ከፍተኛ ኃላፊነትን ለመቀበል የበቁት፤ በራሳቸው ብርቱ ጥረትና ትጋት መሆኑን መገንዘብ ይቻላል።

ተፈሪ መኰንን፤ ባለሙሉ ሥልጣን እንደራሴና አልጋ ወራሽ በነበሩበት ዘመን፤ ቀጥሎም ንጉሠ ነገሥት ሆነው ዘውድ ከጫኑ በኋላ፤ የፋሽስት ጣልያን ኢትዮጵያን እስከ ወረረበት ጊዜ ድረስ፤ መኰንን ሀብተወልድን በማቅረብ በተለያዩ ወቅቶች፤ ከአገር ግዛት ዋና ጸሐፊነት በኋላ፤ የእርሻና የሥራ ሚኒስቴር፣ የገንዘብና የንግድ ሚኒስቴር ዋና ዲሬክተር አድርገው እንደ ሾሟቸው ይታወሳል። በተለይም፤ የንግድ ሚኒስቴርን ከበላይ ሚኒስትር ሳይኖርባቸው በተጠባባቂነት ሲመሩ የቆዩ በመሆናቸው፤ ነፃነት ከተመለሰ በኋላ፤ የእርሻ፣ የንግድና ኢንዱስትሪ ሚኒስትር ተብለው ሲሾሙ፤ ለመኰንን ሀብተወልድ እነዚህን ሁሉ መሥሪያ ቤቶች ከጦርነቱ በፊት ስለሠሩባቸው፤ እንግዶች አልሆኑባቸውም። እነዚህን ሁለት ሚኒስቴሮች እየመሩ ለስድስት ዓመታት ያህል በቆዩበት ዘመን፤ እንደ ወዳጃቸው ጸሐፌ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ሥልጣናቸው የገነነ ሆኖ ለሕዝብ የሚታይ አልነበረም። ብዙ ሰዎች ወልደጊዮርጊስን "አጅሬ" እያሉ በመሠየም፤ በሩቅ ሲፈሩና ሲርበተበቱ፤ መኰንን ሀብተወልድን ያለ አንዳች ችግር የሚያስቡትን ሆነ የሚፈልጉትን ለመግለጽ ሲደፍሩ ይታዩ ነበር። የዚህም ምክንያት፤ የአቶ መኰንን የሥልጣን አሠራርና የአኗኗር ሁኔታ ከሌሎቹ በአካያቸው ካሉት ታላላቅ ባለሥልጣኖች ሁሉ የተለየ ከመሆኑም በላይ፤ ከሕዝብ የሚቀርቡላቸውን አቤቱታዎች፤ በማናቸውም ጊዜና ቦታ መቀበልና ባለጉዳዮቹን ሳይሰለቹ በትዕግሥት ማዳመጥ ዋና ተግባራቸው በመሆኑ ነው፤ የሚል ግምት ተሰጥቶታል። ይህንንም የአቤት ባዮቹን ጉዳይ የሚያከናውኑት በቢሮአቸውና በሥራ ሰዓት ብቻ ሳይሆን፤ በትርፍ ጊዜያቸው በመኖሪያ ቤታቸው ጭምር ነበር። ከዚህም በቀር ዘወትር በየሳምንቱ እሁድና እንዲሁም የሕዝብ በዓላት በሆኑት ቀናቶች ራሳቸው አቋቁመው በሚመሩት በአገር ፍቅር ማህበር ጽሕፈት ቤታቸው ከጠዋት እስከ ማታ እየተገኙ፤ የሚያነጋግሩት አቤት ባይና ችግሩንም በትዕግሥት አዳምጠው መፍትሔ የሚሰጡለት ባለጉዳይ እጅግ ብዙ ነው። አቤት ባዮቹ ከሚያቀርቧቸው ማመልከቻዎች ለመረዳት እንደ ተቻለው፤ ከመቶ ዘጠና አምስቱ (95%) " ... ፍርድ ስለተጓደለብን ማመልከቻችንን የሚቀበለን ስለአጣንና፤ ችግሩ በዝቶብን ከባድ አደጋ ላይ ለመውደቅ ተቃርበናል .... " የሚል ነው። በአብዛኛዎቹ ማመልከቻዎች ላይ የተገለጹትን ለምሳሌ ያህል ለመጥቀስ፤ " .... አገረ ገዥው አለፍርድ አለሕግ ከርስቴ ላይ ነቅሎ አባረረኝ .... " ወይም ደግሞ፤ " ... በ ... ከተማ የሚገኘውን ቤቴንና ንብረቴን አገረ ገዥው ነጥቆ ሂድ ከዚህ ጥፋ ብሎ አባረረኝ። .... እንዲሁም፤ " .... ባላሰብኩትና በማላውቀው ምክንያት መንግሥት ከመደበኝ ሥራዬ ላይ አስተዳዳሪው አስወጥቶ ባዶ ሜዳ ላይ ጣለኝ .... " " ... እንግዲህ ምን ይብጀኝ ? ... እኔስ ለምኜም ሆነ ተሸክሜ ወስፋቴን

የምዘጋበት አላጣም። ግን የጨነቀኝና የሚያሠቃየኝ ራስ ያልቻሉ እምስቱን ልጆቼን ምን ላድርጋቸው? ብዬ ነው ..... " በዚህ አኳኋን የተፈጸመበትን ግፍና የደረሰበትን ችግር አቤቱታ አቅራቢው በጽሑፍና በቃል በመግለጽ ብቻ ሳይወሰን፤ በፊቱ ላይ የሚያወርደውን የእንባ ጉርፍ ሲመለከቱ፤ አቶ መኰንን በኃዘን ምን ያህል እንደሚሠቃዩ ይታይባቸው ነበር። አንዳንዶቹ አቤት ባዮች በአዲስ አበባ የሚያርፉበት ዘመድ በማጣት፤ እጅግ የተጐዱና በምግብ የታረዙ መሆናቸውን አቶ መኰንን ሲያዩ፤ እዚያው አገር ፍቅር ማህበር ግቢ ውስጥ ጊዜያዊ መጠለያ ተሰጥቷቸው ምግብና ልብስ እንዲታደላቸው ያደርጋሉ። አንዳንዶቹ ደግሞ ለጊዜያዊ ማረፊያ ዘመድ ቢኖራቸውም፤ ለአቤቱታቸው ተገቢውን ውሳኔ እስከሚያገኙበት ጊዜ ድረስ እንዳይቸገሩ፤ ለስንቅ የሚሆናቸው ገንዘብ ይሰጣቸዋል። በተለይ አቶ መኰንንን፤ እጅግ የሚያሳዝናቸው ጥፋተኛ ተብለው ከሥራቸው የተነቀሉትና በዚህም ምክንያት ልጆቻቸው ተርበው የሚያለቅሱትን ሲያዩ ነው። አቶ መኰንን በሕይወት ዘመናቸው ሲከተሉት የኖሩት መሠረታዊ ዕምነታቸው፤ አንድ የመንግሥት ሠራተኛ ጥፋት አድርሶ ከሥራው እንዲባረር ፍርድ ከመስጠት በፊት፤ ይህ ሰው የሚያስተዳድራቸው ልጆችና ቤተሰቦች ያሉት መሆን አለመሆኑን ማጣራት ያስፈልጋል፤ የሚል ነው። በአቶ መኰንን አስተያየት፤ የተፈረደበት ሠራተኛ ራስ ያልቻሉ ልጆች ያሉት ከሆነ፤ እሱ ባጠፋው ልጆቹ ለምን ችግር ላይ ይወድቃሉ ? ባይሆን ጠባዩን እስከሚያሻሽል ድረስ ለተወሰነ ጊዜ መጠነኛ የደሞዝ ቅጣት ይደረግበታል እንጂ፤ ከሥራው ተነቅሎ ባዶ ሜዳ ላይ መውደቅ የለበትም። ይህንን አቶ መኰንን የሚያምኑበትን አሠራር፤ ብዙዎች ኃላፊዎች የሚቀበሉት ሳይወዱ በግዴታ ቢሆንም፤ ከጊዜ ብዛት አስተሳሰቡ በሰብዓዊ መንፈስና በሰው ልጅ መብት ላይ የተመሠረተ መሆኑን ተገንዝበውታል። ከዚህ በቀር ደግሞ ሌሎቹን የመንግሥት ባለሥልጣኖችን ያስገርማቸው የነበረው፤ አለቃና ጭፍራ ሳይግባቡ ችግር በሚፈጠርበት ጊዜ ነበር። አቶ መኰንን በግላቸው ባወጡት የአስተዳደር ደንብ፤ አለቃና ጭፍራ ሲጣሉ ሁለቱም ወደ ሚኒስትሩ ቢሮ ሄደው፤ ያልተግባቡበትን የየራሳቸውን አቋም ካስረዱ በኋላ፤ ሚኒስትሩ ይወስኑላቸዋል እንጂ፤ አለቃው በሥልጣኑ የበታቹን እንደአሰኘው መቅጣት አይፈቀድለትም። አቶ መኰንን ይህንን የመሳሰለውን አሠራር የተከተሉት፤ ስለ ሠራተኞች መብት ጉዳይ በስደት ፈረንሣይ አገር በኖሩበት ዘመን በተመለከቱትና ባጠኑት መሠረት መሆኑ ታውቋል። በሠለጠኑት አገሮች፤ አንድ በመንግሥት የተቀጠረ ሠራተኛ፤ በችሎታው እጥረት ወይም ባደረሰው ጥፋት፤ የሚያስቀጣውና አስፈላጊም ከሆነ ከሥራ የሚያስወግደው፤ በመንግሥት ሠራተኞች ማስተዳደሪያ ደንብ (ሲቪል ሰርቪስ) መብቱ ተጠብቆለት ጉዳዩ በጉባኤ ከታየለት በኋላ ነው እንጂ፤ የበላይ አለቃው ሚኒስትር ሆነ ዲሬክተር፤ ብቻውን በወሰነው አይደለም። በኢትዮጵያችን ከመንግሥቱ ንዋይ ኩዴታ በኋላ፤ ሲቪል ሰርቪስ የተባለው የመንግሥት ሠራተኞች ማስተዳደሪያ መሥሪያ ቤት እስከ ተቋቋመበት እንደ ኢ.ት.አቆ እስከ 1954 ዓ.ም ድረስ፤ በእያንዳንዱ የሚኒስቴር መሥሪያ ቤቶች የተቀጠሩት የመንግሥት ሠራተኞች፤ አለቆቻቸው እንደፈለጉ በመቅጣትና ከሥራ ገበታቸው ላይ በማባረር፤ ብዙ በደል ይፈጸምባቸው እንደነበረ፤ ታሪክ ያስታውሳል።

እንግዲህ! ጉዳዩን ለማጠቃለል፤ የመኰንን ሀብተወልድ የሥልጣን አጠቃቀምና የአሠራር ዘዴ፤ ከታላላቅ ባለሥልጣኖች የተለየ የሚያደርገው የውሳኔው አሰጣጥ ዘወትር ለድሃው ወገን የሚሰለፍ ሆኖ በመገኘቱ ነው።

ይኸውም፡- አንደኛ፤ አንድን ሠራተኛ በጥፋት ከሥራው ከማሰናበት በፊት፤ በእሱ ኃላፊነት የሚተዳደሩ ልጆችና ቤተሰቦች መኖር አለመኖራቸው በቅድሚያ እንዲታወቅ አስፈላጊነቱን፣

ሁለተኛ/ በሥራ ላይ አለቃና ጭፍራ የማይግባቡ ሆነው ከተጣሉ፣ ሚኒስትሩ የሁለቱንም አቋም በእኩል ደረጃ አዳምጦ ይወስናል እንጂ፣ አለቃው እንደፈለገው በጭፍራው ላይ ቅጣት መፈጸም እንደማይቻል፣ አጠንክሮ የሚከላከል መሆኑ ነው።

## በአስተዳደር ሥርዓት ላይ የመኰንን ሀብተወልድ ልዩ አቋም !

" ..... አንድ አለቃ ለበታቾቹ የሚሰጠው ትዕዛዝ የሚከበርለት፣ መጀመሪያ እሱ ራሱ አርዓያ ሆኖ ተግባሩን በትክክል መፈጸሙ ሲታይለት ነው እንጂ፣ እሱ እየተንደላቀቀ ጭፍሮቹ ሲደክሙ አይደለም ..... "

መ.ሀ

" ..... በሥራ ላይ ጥፋተኛ የሆነውን ሠራተኛ መቅጣት የተገባ ነው። ነገር ግን፣ ቅጣቱ ከሥራው ገበታ እንዲታገድ የሚያደርገው ከሆነ፣ ከውሳኔው በፊት የሚያስተዳድራቸው ልጆችና ቤተሰቦች መኖር አለመኖራቸው መጣራት አለበት። ሠራተኛው ደሞዙ ሲቆም፣ ራስ ያልቻሉትን ልጆቹን ማስራብ፣ የነገዎቹ በሆኑት በኢትዮጵያ ልጆች ላይ መፍረድ ነው .... "

መ.ሀ.

መኰንን ሀብተወልድ፣ በዚህ ዓለም በኖሩበት በስድሳ ሰባት ዓመት ዘመናቸው ውስጥ፣ የተመቸ ሕይወት ያላቸው ሰው አልነበሩም። ይኸውም፣ በማጣት ወይም በመቸገር ሳይሆን በራሳቸው ፍላጐት ብቻ መሆኑ የታወቀ ነው። የቤተሰብ ታሪካቸውና አስተዳደጋቸው ሲታይ፣ አባታቸው አለቃ ሀብተወልድ በአድዓ ወረዳ በደንቢና በጨለባ ሁለት ጋሻ ለም የሆነ የጤፍ መሬት ስለሚያሳርሱ፣ የኑሮ ደረጃቸው ከፍ ያለ ከመሆኑ በስተቀር፣ ችግር አልነበረባቸውም። ራሳቸው አቶ መኰንንም፣ ዕድሜያቸው ደርሶ በሥራ ዓለም ከተሠማሩ በኋላ የወር ቀለብ ስለነበራቸው፣ ከአባታቸው የእህል ገቢ ጋር ኑሮአቸውን ምቹ ለማድረግ ይችሉ ነበር። ነገር ግን፣ አኗኗራቸውን የተመጠነ በማድረግ ከጓደኞቻቸው የተለዩ ሆነው የታዩት፣ እንደተባለው በራሳቸው ፍላጐት እንጂ፣ በሌላ ምክንያት አለመሆኑን ማመን ይቻላል።

አቶ መኰንን ዕድሜያቸውን በሙሉ በጣም ከሲታ ሆነው የኖሩ ናቸው። ምግብ አይደፍሩም። ሥጋና ቅባት ጨርሶ አይወዱም። ከንጹሕ ውሃ በስተቀር፣ አልኮልና አልኮል ነክ የሆኑትን መጠጦች አይቀምሱም። የዘወትር ምግባቸው እንደ ጕመን የመሳሰሉት የቅጠላ ቅጠል አታክልቶችና ሾርባ፣ እንዲሁም በመጠኑ የሩዝ ቅቅል ሲሆን፣ በቀን ሁለት ሦስት ጊዜ አዘውትረው የሚጠጡት ሻይ ስኳር

ሳይገባበት ነው። በመኖሪያ ቤታቸው አልፎ አልፎ ወዳጃቸውን ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስን ካልሆነ በስተቀር፣ ሌሎቹን አይጋብዙም። እሳቸውም ግብዣ ተቀብለው የሚሄዱት እኝሁ ወዳጃቸው ጸሐፊ ትዕዛዝ ቤት ብቻ ነበር።

የቤተሰብን ደህንነት ለመጠየቅ፣ ወይም በዋና ዋናዎቹ የሕዝብ በዓላቶች መልካም ምኞት ለመግለጥ አቶ መኰንን መኖሪያ ቤት የሚመጣ ቤተዘመድ ሆነ ወዳጅ አልነበረም። በአቶ መኰንን ዕምነት ይህን ለመሳሰለው ጉዳይ በስልክ መነጋገር ይበቃል። ይሁን እንጂ፣ ለሥራ ጉዳይ ከሆነ፣ ማንንም ሰው በማናቸውም ሰዓት ለመቀበል የቤታቸው በር ክፍት ነው። ከቢሮ ሰዓት ውጭ፣ ማለት ከአሥራ ሁለት ሰዓት በኋላ፣ ውሳኔ ያልተሰጣቸውን ልዩ ልዩ ጉዳዮች በልዩ ልዩ ዶሴ እየለዩ ተሸክሞ እቤታቸው የሚያመጣላቸውን ሠራተኛ፣ አቶ መኰንን የሚቀበሉት በሞቀ አነጋገርና በደስታ ነበር። " .... **ማለፊያ ነው። ይህንን ሁሉ በዛሬው ሌሊት አጥንቼ መልሱን ጠዋት አስታውቅሃለሁ** ... " ብለው ያሰናብቱታል። ከምሽቱ ሁለት ሰዓት እስከ ሌሊቱ ሰባት ሰዓት ድረስ፣ የአቶ መኰንን የምሽትና የሌሊት የሥራ ሰዓቶች ስለሆኑ፣ ዶሴዎቹን በርከት አድርጎ የሚያቀርብላቸውን ሠራተኛ መልካም ግብዣ ወይም መልካም ስጦታ እንደሰጣቸው በመቁጠር ያመሰግኑታል። እንቅልፍ የሚይዛቸው ከሌሊቱ ልክ ሰባት ሰዓት ቢበዛ እስከ ንጋቱ አሥራ አንድ ሰዓት ድረስ ብቻ ስለሆነ፣ አንዳንድ ጊዜ የሚያጠኑት ዶሴ ሲያልቅባቸው፣ ሠራተኞቻቸውን በስልክ እየቀሰቀሱ የሥራ ጉዳይ በመጠየቅ ያስቸግራሉ። ብልጥ የሆኑት አንዳንዶቹ ሠራተኞች ስልካቸውን ክፍት በማሳደር፣ ጠዋት ሲገቡ ስልኩ ተበላሽቶብናል ወይም ተቆርጦብናል ብለው ያመልጣሉ።

በጤና በኩል አቶ መኰንን ከልጅነታቸው ጀምሮ የአስም ሕመም ስለአለባቸው፣ በተለይ በብርድ ወቅት እየተነሣ ያሠቃያቸዋል። በዚህ ጊዜ እቢሮ መሄድ ቢያቅታቸውም፣ እቤታቸው ተኝተው ሥራቸውን በስልክ ሲያከናውኑ ውለው ያድራሉ። ለሕመምተኞች መታከሚያ የሚሆን በተፈለገ ዓይነት የሚታጠፍና የሚዘረጋ የሆስፒታል አልጋ ስላላቸው፣ እዚያ ላይ ወገባቸውን ያሳርፋሉ። በዚህ ጊዜ እሳቸው ያሳደጓቸውና ያሠለጠኗቸው ሁለት ወጣቶች ከራስጌያቸው ከቀኝና ከግራ ቆመው፣ አንደኛው የሚያነቡትን ፋይል እየዘረጋ ሲያቀርብላቸው፣ ሌላው ደግሞ ከውጭ የሚደወልላቸውን ስልክ እየተቀበለ፣ እሳቸው የሚፈልጉትንም ሰው እየደወለ ያገናኛቸዋል። የአስሙ ሕመም ተቀስቅሶ ሳል ሲያስቸግራቸው፣ ይታገሉታል እንጂ ሥራውን አቋመው ወደ መኝታ አያዘነብሉም። በዚህ በሚተኙበት አልጋቸው አጠገብ ሁለት ቀጥታ መስመር ያላቸው ቴሌፎኖችና አንድ ቁጥሩ የማይገለጽ ቀለሙ ነጭ የሆነ ቴሌፎን አላቸው። እንደሚባለው፣ ይህ ከቤተመንግሥቱ ማዘሪያ ጋር በልዩ መስመር የተዘረጋው ነጭ ቴሌፎን፣ ጃንሆይ ሲፈልጓቸው ወይም ደግሞ እሳቸው ጃንሆይን ማነጋገር ሲፈልጉ በቀጥታ የሚነጋገሩበት ስለሆነ፣ ማንም አያውቀውም።

ቀደም ሲል እንደተገለጸው፣ አቶ መኰንን እንቅልፍ የሚይዛቸው በሕመም ላይ በሚሆኑበት ሆነ ወይም በደህናው ጊዜያቸው፣ ከሌሊቱ ሰባት ሰዓት እስከ አሥር ሰዓት ወይም ደግሞ ቢበዛ እስከ አሥራ አንድ ሰዓት ድረስ ብቻ ነው። በእነዚህ ሰዓቶች ውስጥ፣ ከውጭ ስልክ ሲደወልላቸው በእንቅልፍ ላይ ስለሚገኙ፣ ስልኩን የሚያነሡት ከሦስት ወይም ከአራት የደወል ጥሪ በኋላ ነው። ከሌሊቱ ከሰባት ሰዓት በፊት ከሆነ ግን፣ ካልታመሙ በስተቀር፣ በአንድ የደወል ድምፅ የስልኩን ማዳመጫ ያነሡና፣ "እኔ ነኝ መኰንን ሀብተወልድ" ብለው መልስ ይሰጣሉ። በመሥሪቱ ስልክ የሚደውሉላቸው ሠራተኞች እንደ እሳቸው ትጉሆቹና

ብርቱዎቹ ካልሆኑ በስተቀር፣ ሌሎቹ የሥራ ጫና ያበዙብናል በማለት አይደውሉም ነበር።

የመኰንን ሀብተወልድ የሥራ ጠባይና አኗኗር እንደዚህ መሆኑን ለመጀመሪያ ጊዜ ለሚሰሙ ሰዎች፣ ምክንያቱን ለመገንዘብ ግራ እንደሚገባቸው አይጠረጠርም። የመጀመሪያ ጥያቄያቸውም፣ ሚኒስትርነት ይህን ያህል ራስን ጉድቶ መሥዋዕት መሆን ያስፈልጋል ወይ ? የሚል ይሆናል። ይህ ሁኔታ የተለየ የመኰንን ሀብተወልድ ጠባይ እንጂ፣ የሁሉም ሚኒስትሮች አይደለም። መጀመሪያ የአልጋ ወራሽ ተፈሪ መኰንን ቀጥሎ የንጉሠ ነገሥት ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ታማኝ ሆነው፣ የዐርባ ሰባት ዓመታት አገልግሎት ያበረከቱት መኰንን ሀብተወልድ፣ ያለ ዕረፍት ሌትና ቀን የሚሠሩት በይፋ ተወስኖ የተሰጣቸውን የሚኒስቴር መሥሪያ ቤቶችን ብቻ በመምራት አልነበረም። ጠቅላላ የመንግሥቱን አስተዳደር በሚመለከቱ ጉዳዮች ሁሉ ድንበር ሳይገታቸውና የሥራ ሰዓቶችም ሳይወስኗቸው፣ ችግሮች ሳጋጠሟቸው የሥራ መስኰች ሁሉ መፍትሔ በመፈለግ መሪያቸውን የሚረዱ ነበሩ። ንጉሠ ነገሥቱም በበኩላቸው፣ በመኰንን ሀብተወልድ ዘዴና መላ ዐዋቂነት ስለሚተማመኑ፣ በልዩ ልዩ መሥሪያ ቤቶች እርምጃ ሳይወሰድባቸው የተወዘፉትን ሥራዎች፣ እንዲሁም በበጀት ችግርና በሠራተኛ እጥረት ምክንያት ሳይፈጸሙ የቀሩትን ፕሮጀክቶች፣ አጥንተው መፍትሔ እንዲያቀርቡላቸው የሚያዙት እሳቸውን ነበር። ይህ ዓይነቱ አሠራር፣ መኰንን ሀብተወልድን እንኳንስ በጓደኞቻቸው ሚኒስትሮች ቀርቶ፣ የመንግሥት ሹማምንቶች በሆኑት ዘንድ ሁሉ፣ የተጠሉ አድርጓቸዋል። መኰንን ግን የሚሠሩት ቀዳማዊ ኃይለሥላሴን ቅር የሚያሰኝ አይሁን እንጂ፣ ሌሎች ለሚሰጡት የነቀፋ አስተያየት ጉዳያቸው አልነበረም። ዕምነታቸውም፣ የኢትዮጵያን ሕዝብ ከጨለማው ዓለም ለማውጣትና ወደ ብርሃን ለማሻገር የሚችሉት ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ብቻ ስለሆኑ፣ እሳቸው ለሚያደርጉት ጥረት፣ መሥዋዕት ሆኖ መካፈልን እንደ ተግባር ብቻ ሳይሆን እንደ ግዳጅ አድርገው ይቆጥሩት ነበር።

አቶ መኰንን በሕይወት ዘመናቸው ሲጨነቁና ዕንቅልፍ አጥተው ሲሠጉበት የኖሩት፣ በሁለት ዋና ዋና ጉዳዮች ላይ ነበር። የመጀመሪያው የኢትዮጵያ ሕዝብ በጐሣና በሃይማኖት ተከፋፍሎ አንድነታችን እንዳይፈርስና ታላቋ ኢትዮጵያ እንዳትጠፋ ሲሆን፣ ሁለተኛው ደግሞ፣ በአንዳንድ በታዳጊ አገሮች ላይ ሲደርስ እንደሚታየው፣ የወታደሮች ኩዴታ ተነሥቶ እናሻሽላለን በማለት፣ እስከዛሬ ድረስ ለብዙ ዓመታት የተደከመበት ሁሉ እንዳይወድም መጠንቀቅ አለብን የሚል ነው። እነዚህ ሁለት ዋና ዋና ነገሮች በአዕምሮአቸው ተቀርጸው የሚኖሩ በመሆናቸው፣ አደጋዎቹ እንዳይደርሱ ለመከላከል፣ የመኰንን ሀብተወልድ የሌት ተቀን ጥረት እስከ ዕለተ ሞታቸው ሳያቋርጥ የኖረ ነበር።

ከሁሉ በፊት ለኢትዮጵያ ሕዝብ፣ አንድነት ምን ያህል እንደሚያስፈልገው፣ መለያየት ምን ያህል እንደሚጐዳው፣ ተባብሮ መሥራትና አገር ማልማት የቱን ያህል እንደሚጠቅመው፣ በአገር ፍቅር ማህበር አዳራሽ በየሳምንቱ እሁድና በሕዝብ በዓላት እየተገኙ ጣዕም ባለው ንግግር ሕዝቡን ማስተማርና ማስረዳት ዋና ተግባራቸው አድርገው ይሠሩበት ነበር። የአገር ፍቅር ማህበር ድርጅትም መሥራቹ መኰንን ሀብተወልድ በሚገልጹት መንፈስ ላይ ተመርኩዞ፣ የኢትዮጵያን ሕዝብ አንድነትና ታሪክ፣ በቴያትር መልክ እያዘጋጀ ከልዩ ልዩ አስደሳች ዜማዎች ጋር በተዋቡ ተወናዋኞች የሚያቀርባቸውን ትርዒቶች ለመመልከት፣ የሚሰበሰበው ሕዝብ ብዛት ሥፍር ቁጥር አልነበረውም። በዚህ ለሕዝብ በሚዘጋጀው ፕሮግራም

ፍጻሜ ላይ አቶ መኰንን የሚያደርጉትን ንግግር ተመልካቹ የሚያዳምጣቸው በቁም ነገርና በረጋ መንፈስ ነበር።

" .... እኛ ኢትዮጵያውያኖች፣ ፈጣሪያችን የሚወደን፣ ንጉሠ ነገሥታችን እንደ ልጆቻቸው የሚያስቡልን፣ የታደልን ሕዝቦች ነን። የምንወዳት አገራችንም፣ በተፈጥሮዋ ሀብታም ስለሆነች፣ እኛ ልጆቿ ተባብረንና ተግተን ብናለማት፣ የምትለግሠን የተመቸ ሕይወት በሥልጣኔ ከገፉት ከፈረንጆቹ አገሮች የተሻለ እንጂ፣ ያነሰ አይሆንም። ፈረንጆች በሥልጣኔ ቀድመውን እኛ ወደ ኋላ ቀርተናል ብለን ኃዘን ይሰማን ይሆናል። በማዘንና በመቆጨት የምናገኘው ጥቅም የለም። ነገር ግን፣ መንፈሳችንን አንቅተን፣ እኛም እንችላለን፣ ከማንም አናንስም ብለን፣ በሕብረት ለመሥራት ቆርጠን ከተነሣን፣ ፈረንጆቹ የደረሱበትን ደረጃ መድረስ አያቅተንም።

.... ፈረንጆቹ፣ ከከፍተኛው የሥልጣኔ ደረጃ ለመድረስ የበቁትና ጸጋ የተመላው ሕይወት ለማግኘት የቻሉት፣ ብዙ ፈተናዎችንና መከራን አሳልፈው ነው። ከሁሉ በፊት በየአገራቸው ያለው የአየር ጠባይ፣ የሰው ልጅ የሚኖርበትና በሰላም ሕይወቱን የሚያሳልፍበት አልነበረም። በክረምቱ ወራት ብርዱና በረዶው እንደ ሲኦል እያሠቃያቸው፣ በበጋው ሙቀቱ እንደ ገሀነም እሳት እያቃጠላቸው መኖር ስላልቻሉ፣ ከብዙ ዘመናት ትግልና ጥረት በኋላ፣ ለብርዱ ማሞቂያውን፣ ለሙቀቱ ማቀዝቀዣውን ሠርተው፣ ችግሩን ለመቋቋምና የተሻለ ሕይወት ለማግኘት በቅተዋል። እኛ ግን ይህ ሁሉ ፍዳ የለብንም። በአየር ጠባይዋ ገነት የሆነች፣ በተፈጥሮ ሀብቷ ለም የሆነች የተቀደሰች አገር አለችን። የሚያስፈልገን አንድነታችንን አስተባብረን ማልማትና በውጤቱ መጠቀም ብቻ ነው።

..... ልብ ብለን ብንመለከተው፣ ፈረንጆች በየጊዜው እየተነሡ ነፃነታችንን ለመድፈርና አገራችንን ለመያዝ የሚጥሩት፣ ያለን የተፈጥሮ ሀብትና ያለን የተመቻቸ የአየር ጠባይ እያጓጓቸው ነው እንጂ፣ ሌላ የተለየ ምክንያት ኖሮዋቸው አይደለም። እንደምታውቁት፣ ከጥቂት ዓመታት በፊት አገራችንን ቅኝ ግዛቱ አድርጎ ለመያዝ የመጣብንን የጣልያን ጠላት ብዙ መሥዋዕት ተቀብለን፣ በብዙ መከራና ትግል ነፃነታችንን አስመልሰናል። ይሁን እንጂ፣ ነፃነታችንን አሸንፈን በመመለሳችን መንፈሳችን ቢጽናናም፣ ጠላቶቻችን ለነገውም ሆነ ለተነገወዲያ እንደማይተኙልን ነቅተን መጠባበቅ አለብን። ስለዚህ፣ ምንድን ነው የሚሻለን? በእኔ አመለካከት፣ ከሁሉ በፊት ካለፈው ስሕተታችን በመማር፣ ሁላችንም ኢትዮጵያዊነታችንንና አንድነታችንን በማጠንከር፣ ጠላት የማይበግረን ሆነን መገኘት አለብን። ይህን መሠረት ጨብጠን ከተባበርንና ቆርጠን ከተነሣን፣ ሁላችንም በየፊናችን፣ ሠራተኛው በሥራው፣ ሞያተኛው በሞያው፣ ነጋዴው በንግዱ፣ ገበሬው በምርቱ፣ አዋቂው በዕውቀቱ፣ ድሃው በጉልበቱ፣ በምንችለውና በሚቻለን ለኢትዮጵያ ሕዝብ አንድነትና ዕድገት የአቅማችንን በመለገስ፣ አገራችን ማንም የማይነካት፣ ማንም የማይደፍራት ሆና ንጉሠ ነገሥቷ የዘረጉላትን የሥልጣኔ ጉዳና ይዛ በመገስገሥ፣ ጠላቶቿን ሁሉ ለመቋቋም ትበቃለች።

..... እንግዲህ ምን እንጠብቃለን? ንጉሠ ነገሥታችን አገራችን የጋራችን፣ ሃይማኖታችን የግላችን መሆኑን አጠንክረው አስተምረውናል። ስለዚህም፣ ዕምነታችንና አምልኮታችን በየግላችን ሆኖ፣ ይህችን ዘለዓለማዊት የሆነችውን አገራችንን ነፃነቷን ለመጠበቅ፣ ልማቷን ለማፋጠን፣ በምትሰጠን ፍሬ ለመጠቀም፣



ንጉሠ ነገሥቱ የኢትዮጵያ ሕዝብ የአገር ፍቅር ማህበር ስለ ንግሥ በዓላቸው ባዘጋጀላቸው
የምሽት በዓል ተገኝተው፤ ፕሬዚዳንቱን አቶ መኰንን ሀብተወልድን ሲያነጋግሩ፤

ዕድሉ እጃችን ላይ ስለሆነ፤ ዛሬ ሥራችንን መጀመር አለብን። ነገ ይመሽና ያቅተናል ..... "

መኰንን ሀብተወልድ በ.ሀ.ፍ.ግ.
ሚያዝያ 28 ቀን 1948 ዓ.ም
ካደረጉት ንግግር የተወሰደ

ፋሽስት ከአገራችን ተባርሮ ነፃነታችን ከተመለሰ በኋላ፤ እንደ ኢት. አቆ. ከ1934 ዓ.ም ጀምሮ መኰንን ሀብተወልድ በመንግሥቱ ንዋይ ኩዴታ እስከ ተገደሉበት እስከ ታህሣሥ 1953 ዓ.ም ድረስ፤ ለአሥራ ስምንት ዓመታት ያለማቋረጥ በየሳምንቱ እሁድና በየበዓላቱ ቀናት በአገር ፍቅር ማህበር አዳራሽ ለሕዝብ ያደረጓቸው ንግግሮች ከዘጠኝ መቶ (900) በላይ እንደተቆጠሩ የዚህ መጽሐፍ ደራሲ ያገር ፍቅር ማህበር ጋዜጦች ዲሬክተር በነበረበት ጊዜ ያስታውሳል። እነዚህ ሁሉ ዲስኩሮች መሠረታዊ ዓላማቸውና መልዕክታቸው፤ **መላው የኢትዮጵያ ሕዝብ የጐሣና የሃይማኖት ልዩነት ሳይሰማው የሁሉም አገር የሆነችውን እንዲት ኢትዮጵያን በአንድነት ዕምነት አልምቶ፤ በአንድነት እንዲጠቀም የሚያሳስቡ ስለሆኑ፤ ከእነዚሁ ውስጥ እሁድ ሚያዝያ 28 ቀን 1948 ዓ.ም የተናገሩትን መርጠን ለምሳሌ ያህል ከዚህ በላይ አቅርበነዋል።**

በዚህ ምዕራፍ ከዚህ ቀደም ሲል እንደተጠቀሰው፤ አቶ መኰንንን ከሚያሳስቧቸው ነገሮች ውስጥ ሁለተኛው ጉዳይ በአንዳንድ አገሮች ኩዴታ እየተባለ በወታደሮች ስለሚወሰደው የመንግሥት ሥልጣን ነበር። እሳቸው በሕይወት በነበሩበት ዘመን፤ በአፍሪካም ሆነ በእስያ እንዲህ እንደዛሬው የኩዴታ አካሄድ የተስፋፋ አልነበረም። የዛሬ ስድሳና አምሳ ዓመታት፤ አንዳንድ ኢትዮጵያውያኖች ከ BBC ዜና እየሰሙ፤ ጉድ ! ጉድ ! ይሉ የነበረው፤ በግብፅ የኰሎኔል ናሥርን የሥልጣን አያያዝና፤ በኢራክ ዤኔራል ካሴም ኩዴታ ሲያደርግ በንጉሡና በንጉሣውያን ቤተሰቦች ላይ የፈጸመውን የጭካኔ አገዳደል ነበር። አቶ መኰንን በዚያን ጊዜ የማስታወቂያን ሥራ የሚመሩ በመሆናቸው፤ በተለይ ይህ በኢራክ የደረሰው አሠቃቂ አድራጐት በኢትዮጵያ ራዲዮና ጋዜጦች እንዳይገለጽ ከልክለዋል። ስለ ኰሎኔል ናሥር ኩዴታ ግን፤ ዜናው በተዳከመ መልክ ተቀምሞ ለኢትዮጵያ ሕዝብ የተገለጸው፤ " ..... **በግብፅ አንድ ዓይነት የአስተዳደር ለውጥ ተደርጐ፤ ንጉሥ ፋሩክም በፈቃዳቸው ቤተሰቦቻቸውን አስከትለው በልዩ መርከብ ወደ ውጭ አገር ሄደዋል ....** " ተብሎ ነው።

እንግዲህ! እንደሚታየው ትክክለኛው ዜና፤ የግብፅ ኦፊሰሮች የንጉሥ ፋሩክን መንግሥት ገልብጠው ሥልጣን መያዛቸውና፤ ንጉሡን ከነቤተሰቦቻቸው አገር ለቅቀው እንዲሰደዱ ማድረጋቸው ነው። ነገር ግን፤ ዜናው በዚህ አኳኋን ለኢትዮጵያ ሕዝብ የተነገረ እንደሆነ፤ ለካስ ወታደሮች ንጉሥ አባርረው የመንግሥት ሥልጣን መያዝ ይችላሉ የሚል ትምህርት ይሰጣል ተብሎ ስለተፈራ፤ በግብፅ አገር አንድ ዓይነት የአስተዳደር ለውጥ ስለተደረገ፤ ንጉሥ ፋሩክም በፈቃዳቸው ወደ ውጭ አገር ሄደዋል፤ የሚል የተድበሰበሰ ዜና ተነገረ። ይህን የመሰለው የፕሮፓጋንዳ አገላለጽ ምን ጥቅም እንደሚሰጥ አይታወቅም። ዜናው እውነቱን ይዞ ቢወጣ መንግሥትን የሚያሳስበው ከሆነ፤ በዚህ መልክ ከሚገለጽ፤ ሳይነገር ቢቀር የተሻለ በሆነ ነበር። የሆነ ሆኖ፤ ፊደል ለቆጠረውና

የብርሃን ጮራ ለፈነጠቀበት ሕዝብ፤ ዕድሜ ለBBC በዓለም ላይ የሚደርሱትን ነገሮች ሁሉ የመስማት ዕድል ስላለው፤ በአገር ውስጥ የዜና ማሠራጫ ድርጅቶች መክልከሉ አይጉዳውም።

እንግዲህ ! መኰንን ሀብተወልድ እንደ ኢት. አቆ. ከ1941 እስከ 1951 ዓ.ም ድረስ ለአሥር ዓመታት የማስታቂያ ሚኒስቴርን በመሩበት ጊዜ፤ በልዩ ልዩ አገሮች በኩዴታ የመንግሥት ለውጥ ሲደረግ፤ ዜናው ለኢትዮጵያ ሕዝብ በጋዜጦችና በራዲዮ እንዲገለጽ የሚፈቅዱት፤ በጣም በተዳከመ መልክ ተቀምሞ መሆኑን ከዚህ በላይ የቀረበው የግብፅ ጉዳይ ምሳሌነቱን አሳይቷል። ይሁን እንጂ፤ በአንዳንድ ረገድ ደግሞ የአቶ መኰንን የፐሮፓጋንዳ አመራር የተለየ ሁኔታ ይታይበታል። ይኸውም ለምሳሌ ያህል፤ እ.ኤ.አ በ1953 ዓ.ም በኢራን ጠቅላይ ሚኒስትር በሞሐመድ ሞሳዲቅ ላይ ስለደረሰው ችግር አቶ መኰንን ያሳዩት ስሜት ነው።

እንደሚታወሰው፤ ሞሐመድ ሞሳዴቅ (Mohmmed Mossadegh) በፓርላማ ፓርቲው የድምፅ ብልጫ አግኝቶ ከ1951 እስከ 1953 ዓ.ም የኢራን ጠቅላይ ሚኒስትር በመሆን መንግሥቱን በሚያስተዳድርበት ጊዜ፤ በአገሩ ላይ ከዐርባ ዓመታት ጀምሮ እንግሊዞች በቁጥጥራቸው ሥር አድርገው የሚጠቀሙበትን የነዳጅ ዘይት ማዕድን፤ ብሔራዊ ሀብት አድርጐ ለኢራን በማውረስ፤ በዓለም ላይ ያልተጠበቀ አስደንጋጭ የሆነ እርምጃ ወሰደ። በዚህ ጊዜ ጥቅማቸው የተወሰደባቸው እንግሊዞች፤ የኢራን ንጉሠ ነገሥት ሻህ ሬዛ ፓህላቪን ይዘው በሞሳዴቅ ላይ በመነሣት፤ በዴሞክራሲ ሥርዓት የተመረጠውን የሞሳዴቅን መንግሥት በወታደር ኃይል ገልብጠው፤ በጄኔራል ዛሂዲ (Zahedi) የሚመራ የዲክታተር መንግሥት አቋቋሙ። ሞሳዴቅ፤ ምንም እንኳ በእንግሊዞች ላይ የወሰደው እርምጃ፤ ለኢራንና ለሕዝቦቿ ጥቅም በማሰብ መሆኑ ታውቆለት በአገሩ ውስጥ ከፍተኛ የሆነ ሕዝባዊ ድጋፍ ቢጐርፍለትም፤ በውጭ መንግሥታት (እንግሊዝና አሜሪካ) ተደግፎ የመጣበትን የወታደራዊውን ኃይል ለመቋቋም አልቻለም። በመጨረሻም ኩዴታ አድራጊው ጄኔራል ዛሂዲ፤ ሥልጣኑን ከጨበጠ በኋላ፤ ሞሳዴቅን ለሦስት ዓመታት ጽኑ እሥራት አስፈረደበት።

የኢትዮጵያ ጋዜጠኞች አባት የተከበሩ ብላታ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ፤ በዚያን ጊዜ የአዲስ ዘመንና የሰንደቅ ዓላማችን ጋዜጦች ዲሬክተር፤ በዚህ በሞሳዴቅ ጉዳይ አቶ መኰንን ሀብተወልድ፤ የገለጹላቸውን አስተያየት እንደሚከተለው አጫውተውኛል።

" .... በዓለም የዜና ማሠራጫ ድርጅቶች ስለ ኢራን ቤንዚንና ስለ ጠቅላይ ሚኒስትሩ ስለ ሞሳዴቅ የሚደርሱንን ሥፍር ቁጥር የሌላቸው ዜናዎች፤ አለቃችን አቶ መኰንን በጥብቅ ሲከታተሉ አይቼ በጣም ተገረምኩ። ወዲያውም ጠጋ ብዬ አንድ ጥያቄ አቀረብኩላቸው። .... የኢራን ጉዳይ ጌታዬን ያሳሰብዎት ይመስላል። መቼም ንጉሠ ነገሥቱ ሻህ የሚሆናቸውን ሰው አግኝተው ሞሳዴቅን ሽረውታል። ከእንግዲህ ወዲህ ምን የሚያሠጋ ነገር አለ ? .... አልኳቸው። መልሱን ወዲያውኑ ሰጡኝ። የደረሰው በጣም የሚያሳዝን ነው። ሞሳዴቅ እኮ፤ ጥቅማቸውን ነጥቆ ያስደነገጣቸው እንግሊዞችን ነው እንጂ ሻሁን አልነበረም። ሻሁ ግን በራሳቸው አገርና በራሳቸው ሀብት ጉዳይ፤ ለእንግሊዞች አጋዥ ሆነው በወታደር ኃይል

በፓርላማ የተመረጠውን ሰው መሻራቸውና በምትኩ ወታደር መሾማቸው፣ በታሪካቸው ላይ ጥቁር ነጥብ እንዳሳረፉበት የሚቆጠር ነው። ደግሞም ካነሣኸው፣ ሞሳዴቅ መቸኮሉና ዘዴኛ አለመሆኑ ነው እንጂ፣ የነዳጅ ዘይቱን ማዕድን ከእንግሊዞች ነጥቆ ያገሩ ሀብት እንዲሆን መሞከሩ የሚያስመሰግነው ነው። እኔን ያሳዘነኝ፣ ይኸ ሰው ለአገሩ ክብርና ለሕዝቡ ጥቅም ሲል የሠራውን እንደ ወንጀል ቆጥረውበት መታሠሩ ነው …. " አሉኝ። አቶ መኰንን በተናገሩት፣ የኢራን ሻህ ያደረጉትን የማይደግፉ መሆናቸውን ሲገልጹልኝ በመጠኑም ቢሆን ደነገጥኩ። ምክንያቱም ይህን የመሰለውን አስተያየት ከእሳቸው የማልጠብቀው በመሆኑ ነው። ወዲያው ጥያቄዬን ቀጠልኩና፣ ጌታዬ ፈቃድዎ ቢሆን በዚህ ጉዳይ በጋዜጦቻችን ላይ ጥቂት ዜና መግለጽ የተገባ ይመስለኛል፣ አልኳቸው። " …. አዎን ! ወሬውን ባጭሩ መግለጽ ያስፈልጋል። ዋናው ቁም ነገር በምን አኳኋን እንደምትጽፈው ነው። እንደ … እኔ … እንደ … እኔ፣ እንግሊዞች ለዐርባ ዓመታት ይዘው ሲጠቀሙበት የነበረውን የኢራን የነዳጅ ዘይት ማዕድን፣ ሞሳዴቅ የተባለው የኢራን ጠቅላይ ሚኒስትር፣ የኢራን ሀብት ነው ብሎ ከእንግሊዞች ላይ ለመውሰድ ያደረገው ሙከራ ሳይሣካለት ቀርቷል …. ብሎ ሐተታ ሳይጨመር በደረቁ መጻፍ ነው። መቸም ቢቻል፣ በኢራን ላይ እንግሊዞች አሁንም የሚያደርጉትን የጥጋብ ሥራ፣ አንድ የእንግሊዝ ዜጋ የሆነ ሰው አስተያየት ጽፎ በጋዜጣችን ላይ ቢታተምለት ጥሩ ነበር አሉኝ።

ብዙ ጊዜ ከወዳጆቼ ጋር ስጨዋወት፣ ጌታዬ ወዳጄ የሆኑትን አቶ መኰንንን፣ ሐሳባቸውንና ዝንባሌያቸውን ከእኔ የተሻለ የሚያውቅ የለም ብዬ እሟገት ነበር። ለካስ በትክክል ያልተረዳሁት ነገር ኖርዋል ! በመሠረቱ የወታደር ኩዴታ የሚባል ነገር አይወዱም። ሆኖም በኢራን ኩዴታውን ያደረጉት ንጉሠ ነገሥቱ ሻህ ራሳቸው በመሆናቸው፣ አቶ መኰንን በመደገፍ ፋንታ ይቃወማሉ ብዬ አልጠበቅኩም። በዚህም አኳኋን ጉዳዩን እንሥቼ ሳነጋግራቸው፣ አስተያየታቸው፣ ለሕዝብ ጥቅም ያዘነበለና የሕዝብ ወገን የሆነውን ሞሳዴቅንም የሚደግፉ ሆነው አገኘኋቸው። ስለዚህ፣ ከእንግዲህ ወዲህ ስለ አቶ መኰንን ያለኝ ዕውቀት እንደ ኢራን በመሳሰለው ጉዳይ፣ ደሃውን ሕዝብ የሚጐዳውንና የሚጠቅመውን እያሰቡ አስተያየት የሚሰጡ እንጂ፣ በኃይልና በጉልበት የሚፈልገውን የሚያደርግ መንግሥት የማይደግፉ መሆናቸውን ተረድቻለሁ …. "

## የኢትዮጵያ ጋንዲ

ብዙ ሰዎች መኰንን ሀብተወልድን ከሕንዳዊው ከማሕተመ ጋንዲ ጋር ያመሳስሏቸዋል። በመሠረቱ አቶ መኰንን ስለ አገር ዕድገት ጉዳይና ስለ ሕዝብ አኗኗር ያላቸው ስሜት ከጋንዲ ዕምነት ጋር የሚቀራረብ በመሆኑ፣ የኢትዮጵያ ጋንዲ ናቸው ቢባል፣ ስሕተት አይሆንም። እንደሚታወሰው፣ ማሕተመ ጋንዲ በዚህ ዓለም በኖረበት በሰባ ዘጠኝ ዓመታት ውስጥ፣ አብዛኛውን የሕይወት ዘመኑን በትግል ያሳለፈው፣ ያለ ሁከትና ያለ ብጥብጥ፣ በሰላም የሕንድን ነፃነት ከእንግሊዞች እጅ ለማላቀቅ ነበር። ከዚህም ጋር እያይዞ የሕንድን ሕዝብ ለማስተማር ብዙ ጥረት ያደረገው፣ ነፃነትን በሰላማዊ ጉዳና አግኝቶ መደሰት ብቻ ሳይሆን፣ ነፃነትም ከተገኘ በኋላ የሕንድ ሕዝብ ባለው አቅምና ባለው ችሎታ



"የኢትዮጵያ ጋንዲ" እየተባሉ የሚጠሩት መኰንን ሀብተወልድ፣ የአገር ልጆች የእጅ ጥበብ ሥራዎችን ለማስፋፋት፣ ከአንድ የውጭ አገር ባለሞያ ጋር ሲወያዩ፣

ያገሩን ሀብት አልምቶ በውጤቱ መኖር እንጂ፣ የኮሎኒያሊስቶቹን የኢኮኖሚ ምርት አለመቀበል ነው የሚል ነበር።

መኰንን ሀብተወልድም እንደ ጋንዲ በሚያደርጉት ጥረት፣ የኢትዮጵያ ሕዝብ አንድነቱን አጠንክሮ፣ የአገሩን ሀብት ተባብሮ በማልማት ራሱን ችሎ መኖር እንጂ፣ የፈረንጆቹን የኢንዱስትሪ ውጤት ተቀባይ መሆን የለበትም ይሉ ነበር። ጋንዲ እንዳደረገው እሳቸውም፣ የኢትዮጵያ ሕዝብ የራሱን ልብስ ሠርቶና ሰፍቶ መልበስ ሲችል፣ ከፈረንጅ አገር የተዘጋጀውን እያስመጣ ሲያጌጥ መታየቱ የሚያሳፍር መሆኑን አጥብቀው መክረዋል። ይህንንም ሐሳባቸውን ምክር በመስጠት ብቻ አልወሰኑትም። እንደ ኢት. አቆ ከ1935 እስከ 1941 ዓ.ም ድረስ ለስድስት ዓመታት የእርሻ፣ የንግድና የኢንዱስትሪ ሚኒስትር በነበሩበት ዘመን፣ በአዲስ አበባ ከተማ "ኮልፌ" በተባለው ሠፈር፣ "ያገር ልጆች የእጅ ጥበብ ማሻሻያ ተብሎ የተሠየመ የሞያ ትምህርት ቤት አቋቁመው፣ ከጥጥና ከሱፍ ልዩ ልዩ ቀለም ያላቸውን ጨርቃ ጨርቆች በማሠራት፣ ሕዝቡ እንዲጠቀምበት ለገበያ እንዲቀርብ አድርገውት ነበር። በተለይ ከሱፍ የተሠሩት ጨርቆች ከፈረንጅ አገር በብዙ ገንዘብ ከምናስመጣቸው ምንም ልዩነት ስለሌላቸው፣ ምሳሌነቱን ራሳቸው በመውሰድ ኮትና ሱሪውን አሰፍተው መልበስ ጀመሩ። ለኢትዮጵያ ሴቶችም፣ ከጥንት ሲያያዝ የመጣው ያገር ልብስ፣ በልዩ ልዩ ሕብረ ቀለም አሸብርቆ እየተሠራ፣ ስፌቱም በዘመናዊ መልክ ሰውነት ላይ የሚቀለጥፍና የደም ግባትን የሚያሳምር እንዲሆን፣ በኮልፌ የእጅ ጥበብ ትምህርት ቤት ሸማኔዎቹና መኪና ሰፊዎቹ ተዘጋጅተው ነበር። ነገር ግን፣ ብዙዎቹ ሴቶች በጨርቁ ጥራትና በስፌቱ ቢደሰቱም፣ እንደ ፈረንጆቹ ቀሚስና እንዲሁም እንደ ኮትና ጉርድ የቀለጠፈና ለቢሮ ሥራ ምቹ የሚሆን አይደለም በማለት፣ ሥልጣኔን የቀመሱት ሁሉ የሚጠበቀውን ገበያ አቀዘቀዙት። ሆኖም አቶ መኰንን በዚህ ተስፋ አልቆረጡም። በዚህ በእጅ ጥበብ ትምህርት ቤት ውስጥ የሚሠሩት ያገር ልብሶችና ጨርቃ ጨርቆች ብቻ ሳይሆኑ፣ ልዩ ልዩ የሥጋጃ ምንጣፎች፣ ያልጋ ልብሶችና መጋረጃዎች፣ ከነዚህም በቀር ከሸክላና ከብረታ ብረት የሚመረቱ ልዩ ልዩ የአገር ባህል ዕቃዎች ስላሉ፣ በሴቶች ልብስ የገበያ እጥረት ምክንያት ተማሪ ቤቱ ጉዳት አልደረሰበትም።

## ጥጥ ትከሉ ! ፍተሉ !

በምርቱ ብዙ ትጠቀማላችሁ፤
አገራችሁንም ታስከብራላችሁ።

የሚለው የመኰንን ሀብተወልድ ጥቅስ፤ በየትልልቁ ሕንፃና በየዋናው አደባባይ በኤሌክትሪክ ብርሃን ተግ-ተግ እያለ፤ የሕዝቡን አዕምሮ ይማርክ ነበር።

ከዚህም በቀር ወደ ራስ መኰንን ድልድይ በሚወስደው በቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ጐዳና ለዘወትር ክፍት የሆን ኤግዚቢሽን ተዘጋጅቶ፤ በተለይ በዘመናዊ ኢንዱስትሪ ከጥጥ የሚገኘውን ምርት ሕዝቡ እየጐበኘ እንዲረዳው ተደርጐ ነበር።

እንግዲህ ! የመኰንን ሀብተወልድ ጥረት የአገራችንን ባህልና ሞያ እኛው ራሳችን በዘመናዊ ስልት እያስፋፋን ካልተጠቀምንበት፤ በኢትዮጵያዊነት ኩራታችን እምን ላይ ነው? በሚል ዕምነት ላይ የተመሠረተ ስለሆነ፤ "የኢትዮጵያ ጋንዲ" የሚያሰኛቸው ይህን የመሳሰለው አስተሳሰባቸው ነው ማለት ይቻላል።

# ክፍል ፲

## ታሪካዊው የጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ

# የሥልጣን ፍጻሜ

# ምዕራፍ ፩

## የወልደጊዮርጊስ ሥልጣን የሚያሠጋ ሆነ

ቀደም ሲል በታየው ምዕራፍ እንደተገለጸው፣ የጸሐፊ ትዕዛዝ ሥልጣን ከነበረበት እጅግ ከፍ እንዲል በንጉሠ ነገሥቱ በተወሰነ ጊዜ፣ በተለይ የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ሚኒስትሮችና አገረ ገዥዎች ምን ያህል ቅሬታ እንዳደረባቸው ይታወሳል። ሁሉም በየግላቸው ለንጉሠ ነገሥቱ ያቀረቡት አቤቱታ፣ የጽሕፈት ሚኒስትሩ የምንሠራውን ሁሉ እየነቀፈ የሚልክልን መምሪያ ከተገቢው ሥርዓት ውጭ ስለሆነ፣ ጃንሆይ ይህንን እንዲያስወግዱልን መሬት ስመን ልመናችንን እናቀርባለን የሚል ነበር።

ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ለአሠራራቸው የተለየ ጥበብና ዘዴ ስላላቸው፣ በጽሕፈት ሚኒስቴር ማዘዣና በንጉሠ ነገሥቱ ማህተም በሚጽፉት ደብዳቤ፣ መልካም ሠርቶ ፍሬውን ላሳየው ምስጋና፣ ሳይሠራ ቀርቶ ጥፋት ላስከተለው ወቀሳና ማስጠንቀቂያ የሚገልጹት፣ በራሳቸው ሐሳብና በራሳቸው አመለካከት ተመሥርተው መሆኑ ባያጠራጥርም፣ ሁልጊዜ የደብዳቤያቸው ማሠሪያ "መታዘዙን አስታውቃለሁ" የሚል ነው። በዚህ አቀራረብ ሚኒስትሮቹም ሆኑ አገረ ገዥዎቹ የጃንሆይ ትዕዛዝ ነው ብለው እጅ ነሥተው ከመቀበል በስተቀር፣ ሌላ ትርጉም መስጠት የማይቻላቸው መሆኑ በግልጽ ታየባቸው። ወልደጊዮርጊስም ተቃዋሚዎቻቸውን ድል ማድረጋቸው ስለተሰማቸው፣ በሥልጣናቸው መሥራቱን ቀጠሉበት።

በዚህ አኳኋን የቀዳማዊ ኃይለሥላሴን ሚኒስትሮችና ጠቅላይ ገዥዎች በቁጥጥራቸው ውስጥ ካስደረጉ በኋላ፣ በሌሎቹ የመንግሥት ሠራተኞች ላይ የሚወስዷቸውን እርምጃዎች ከጊዜ ወደ ጊዜ እያጠነከሩት ሄዱ።

ይኸውም፡-

- ጸሐፊ ትዕዛዝ የሰጡትን መምሪያ ተቀብሉ በተግባር ለማዋል ከመዘጋጀት በስተቀር፣ ተቃራኒ ሐሳብ ለማቅረብ ጨርሶ የማይቻል ሆነ።
- አንዳንድ የጉደለ ወይም የተሳሳተ የሥራ ጉዳይ ሲያጋጥማቸው፣ የሚያደርጉት እርማት እንደ ቀድሞው በለሰለሰ አነጋገር ሳይሆን፣ በቁጣና በብርቱ ማስጠንቀቂያ በመሆኑ፣ የመንግሥት ባለሥልጣኖች ሁሉ ሊቆጣጠሩት የማይችሉት ፍርሃት አደረባቸው።
- በመሠረቱ፣ በማናቸውም የሥራ መስክ ጸሐፊ ትዕዛዝ ያዘዙት ሳይፈጸም ውሎ ማደር የለበትም።
- በማናቸውም የሥራ መስክ መልካም ውጤት ከማምረት በስተቀር፣ ለስህተት ቦታ አይሰጠውም።



ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ የጽሕፈትና የፍርድ ሚኒስትር፤



አቶ መኰንን ሀብተወልድ የገንዘብ ሚኒስትር

- በወልደጊዮርጊስ ዕምነት፤ አንድ የመንግሥት ኃላፊ የተሰጠውን ሥራ በችሎታ እጥረት ምክንያት ተግባሩን መፈጸም ካቃተው፤ ሳይውል ሳያድር ቦታውን ለሚችል መልቀቅ አለበት።
- በወልደጊዮርጊስ አስተያየት፤ አንድ የመንግሥት ኃላፊ ችሎታ ቢኖረውም፤ የአሠራር ዘዴ በማጣት ወይም በስንፍና የሚጠበቅበትን ውጤት ማምረት ከተሳነው፤ የተመደበበትን ቦታ ለጉበዙ ሠራተኛ አስረክቦ ዞር ማለት አለበት።
- በወልደጊዮርጊስ አቋም፤ ሹመት የሚሰጠው ላለው የሥራ ቦታ የሰውየው ችሎታና ልምዱ በቂ ሆኖ ሲገኝ ነው እንጂ፤ የአገልግሎቱን ዘመን እየደመረ በማቅረብ አይደለም።

በዚህ ጉዳይ፤ በወልደጊዮርጊስና በመኮንን ሀብተወልድ መካከል ያለው <u>የአስተዳደር አመራር ልዩነት፤</u> በሁለት ዋና ዋና ጉዳዮች ላይ መሆናቸውን እናያለን። እነዚህም፡-

1ኛ/ አቶ መኮንን ባላቸው መሠረታዊ ዕምነት ከዚህ ቀደም እንደተገለጸው፤ አንድ የመንግሥት ሠራተኛ በችሎታው እጥረት ምክንያት የመንግሥቱ ሥራ ተበድሎ ቢገኝ፤ ሠራተኛው ችሎታው ወደሚፈቅድለት ቦታ ተፈልጎ ይዛወራል እንጂ፤ ከሥራው ታግዶ ቀለቡ ሲቋረጥ፤ በሚያስተዳድራቸው ቤተሰቦቹ ላይ የሚደርሰውን ችግር በቅድሚያ ማሰብ ያስፈልጋል ይላሉ።

2ኛ/ የመንግሥት ሠራተኛ የሆነ ሰው፤ መንግሥትን ሲበድል ካልተገኘ በስተቀር፤ በአቅሙ የሰጠው የአገልግሎት ዘመን በማናቸውም መልክ ለሹመትም ሆነ ለደሞዝ ዕድገት ሊቆጠርለት ይገባል በማለት ይከራከራሉ።

ወልደጊዮርጊስ ግን፤ የመኮንንን ሐሳብ ምንም እንኳ በሰብዓዊነቱ ቢደግፉት፤ የመንግሥት ትልቁ ኃላፊነት ለሕዝቡ ኑሮ መሻሻልና ለጤናው አጠባበቅ የታሰበለትን ፕላን አፋጥኖ መሥራት ስለሆነ፤ ለሥራው ብቁ ያልሆኑትን ሠራተኞች መንግሥት እየተሸከመ፤ ሲቀልብ መኖር የለበትም ብለው ያምናሉ። አቶ መኮንን ለሚጨነቁበትም ጉዳይ በሌላው በሠለጠነው ዓለም እንደሚደረገው ሁሉ፤ ወደፊት በአገራችን የሕዝባዊ ኑሮና የማህበራዊ ሥራ ሚኒስቴር ተቋቁሞ፤ በቤተሰቦች ላይ ለሚደርሱት ችግሮች ሁሉ፤ መፍትሔ እንደሚገኝ ተስፋ ያደርጋሉ።

በሌላ በኩል ደግሞ፤ ቀደም ሲል እንደተገለጸው መኮንን ሀብተወልድን ከወልደጊዮርጊስ የተለዩ የሚያደርጋቸው፤ በአኗኗራቸው ጠባይና የመንግሥት ሠራተኞች በሚሰጧቸው አስተያየቶች ነው። ከዚህ በፊት እንደተገለጸው፤ አብዛኛዎቹ ወልደጊዮርጊስን "እጅሬ" እያሉ በመጥራት በሩቁ ሲፈሯቸውና አጠገባቸውም ሲደርሱ፤ ወባ የመታቻቸው ይመስል እንደዚያ ሲንቀጠቀጡ፤ መኮንን ሀብተወልድን ይዳፈራሉ ባይባልም፤ ፍርሃት አይታይባቸውም ነበር። ወልደጊዮርጊስ ወደቢሮአቸው ሲገቡ፤ ግራና ቀኙን ተሰልፈው እጅ የሚነሷቸው ደጀ ጠኒዎች፤ ከቢሮአቸው ሲወጡም ከኋላቸው የሚከተላቸው አጀብና ከፊታቸው ወደ አውቶሞቢላቸው እስከሚገቡ ድረስ፤ ሽብ ረብ የሚሉት አጋፋሪዎች ለትልቁ ሥልጣናቸውና ለክብራቸው የተለየ መልክ ሲሰጡት ይታይ ነበር። አቶ መኮንን

ደግሞ በዚያች "የድሆች መሸከርከሪያ" እየተባለች በምትጠራ ቮልስ ቫገን አውቶሞቢል ውስጥ ሆነው ፋይል እያነበቡ ወደ ቢሮአቸው ሲገቡና ሲወጡ፣ የሚያጅባቸውና የሚከተላቸው ስለሌላቸው፣ ለተመልካቹ ሕዝብ የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ትልቅ ባለሥልጣን መሆናቸውን መለየት አይቻልም። ከዚህም በቀር በየበዓላቱ፣ ለዘመን መለወጫ፣ ለልደትና ለትንሣኤ "እንኳን አደረስዎ" ለማለት፣ ከቤተመንግሥቱ ቀጥሎ ወደ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ መኖሪያ ቤት የሚጎዘው ባለሥልጣንና የመንግሥት ሹማምንት ሥፍር ቁጥር አልነበረውም። እቶ መኰንን ቤት ግን ለሥራ ጉዳይ እሳቸው የጠሩት ሰው ካልሆነ በስተቀር፣ ለበዓል እንኳን አደረስዎ ለማለት ብቅ የሚል የለም።

በዚህ አኳኋን እንደ ኢት. አቆ. ከ1941 ዓ.ም ጀምሮ በየጊዜው እያደገና እየጐላ የመጣው የአጅሬ ወልደጊዮርጊስ ሥልጣን፣ በ1946 ዓ.ም አጋማሽ ላይ፣ ሹመቱ ለምን ወደ ጠቅላይ ሚኒስትርነት ከፍ አይልም? የሚለው የደጋፊዎች አስተያየት እየተፋፋመ መወራት ጀመረ። ጸሐፊ ትዕዛዝ ራሳቸውም የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ቀኝ እጅ ሆነው ለአሥራ ሦስት ዓመታት በሙሉ ሥልጣን ከሠሩ በኋላ፣ ይኸ ብዙ ሰዎች የሚመኙትና እሳቸውም የሚጠብቁት የጠቅላይ ሚኒስትርነት ሹመት መቼ ነው የሚመጣው? ብለው ሳያስቡ አልቀሩም። እንዲሁም ስለእሳቸው በያለበት የሚወራውንና የሚሰጠውን ትችት ሲያመዛዝኑት፣ ከተቃዋሚዎቻቸው ይልቅ የደጋፊዎቻቸው ቁጥር እየጨመረ ሄዷል የሚል ዕምነት እንደአደረባቸው ታውቋል። እንደ እውነቱም በአንዳንድ ረገድ ሁኔታው ሲታይ፣ ጸሐፊ ትዕዛዝ የደጋፊዎቻቸው ወይም የታዛዦቻቸው ቁጥር እየጨመረ ሄዷል ብለው ቢያስቡ፣ ስሕተት ነው ማለት አይቻልም። ለመቃወም ተነሥተውባቸው የነበሩት አብዛኛዎቹ ጠቅላይ ገዥዎችና ሚኒስትሮች፣ እያደር ነገሩን ሲያጠኑት፣ ከጽሕፈት ሚኒስትሩ ጋር በመጣላት ከሚደርሱባቸው ችግሮች፣ በመግባባት የሚያገኟቸው ጥቅሞች የሚበልጡ መሆናቸውን ስለተገነዘቡት፣ በጠቡ ፋንታ ወዳጅነትን መርጠው ሰላም ለመገንባት ሲሞክሩ ታይተዋል። መቼም እንደሚታወቀው፣ በአገራችን ለድጋፍም ሆነ ለተቃውሞ የሚወሰደው እርምጃ በአቋም ላይ በመመሥረት ሳይሆን፣ እንደሚገኘውና እንደሚታጣው ጥቅም ታይቶ ስለሆነ፣ ይህ ዛሬ በአጅሬ ወልደጊዮርጊስ ላይ የሚያንጸባርቀው የድጋፍ ብርሃን፣ ነገ እንደማይደበዝዝ ወይም እንደማይጨልም ዋስትና የሌለው መሆኑ መታሰብ ነበረበት። የሆነ ሆኖ ጸሐፊ ትዕዛዝ፣ ምንም እንኳ በንጉሣውያን ቤተሰብና በመሳፍንት የተጠመደባቸው ተቃውሞ በቶሎ የሚለወጥ አለመሆኑን ባይስቱትም፣ ከሁሉ በፊት ከንጉሠ ነገሥቱ፣ ቀጥሎም ወዳጆቻቸው ከሆኑት ሚኒስትሮችና ታላላቅ ባለሥልጣኖች በሚኖራቸው ድጋፍ ስለሚተማመኑ፣ ምናልባት ከጽሕፈት ወደ ጠቅላይ ሚኒስትርነት የሚዛወሩበትን ቀን ከመጠበቅ በስተቀር ሌላ ይደርሳል ብለው የሚያስቡት ጉዳይ አልነበራቸውም።

# ምዕራፍ ፪

## የንጉሣዊው ቤተሰብ ተቃውሞ ጠነከረ፤

ምን እስኪደርስ ይጠበቃል?

ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ የቀዳማዊ ኃይለሥላሴን ሙሉ ድጋፍ ይዘው እስከቆዩ ድረስ፤ ሥልጣናቸው ሊቀነስ አይችልም በማለት ተስፋ የቆረጡት ሚኒስትሮችና ጠቅላይ ገዥዎች፤ ከጽሕፈት ሚኒስትሩ ጋር ለመግባባት ሲሞክሩ መታየታቸው ባለፈው ምዕራፍ ተጠቅሷል። ወልደጊዮርጊስም፤ "በእኔ ላይ በጓዳ የቀየሳችሁት የተቃውሞ መንገድ የትም እንደማያዘልቃችሁ ተገንዝባችሁ፤ በአደባባይ ፊት ለፊት ወደ እኔ ለመቅረብ ከወሰናችሁ፤ በደስታ እቀበላችኋለሁ" ብለው ተናግረው ነበር።

በዚህ መሠረት ከጸሐፊ ትዕዛዝ ጋር ተግባብቶ ለመሥራት እርምጃ ከወሰዱት ሚኒስትሮችና ገዥዎች መካከል አንዳንዶቹ፤ ከዚህ በፊት የተደቀኑባቸው ችግሮቻቸው ሁሉ በጥቂት ጊዜያት ውስጥ ስለተወገዱላቸው፤ የጋለ ደስታቸውን በያለበት መግለጥ ጀመሩ። ይህ ዜና እንደተሰማ፤ የንጉሣዊው ቤተሰብ አባሎችና ታላላቅ መሳፍንት፤ በወልደጊዮርጊስ ላይ ያላቸውን ተቃውሞ በፊት ከነበረው የበለጠ አጠነከሩት። የጽሕፈት ሚኒስትሩ አለአግባብ የሚጠቀሙበትን ሥልጣን አንቀበልም በማለት ሲታገሉ የነበሩት ዋና ዋናዎቹ ሚኒስትሮቹና ጠቅላይ ገዥዎቹ አሁን አሜን ብለው እጃቸውን ከሰጡ፤ የወልደጊዮርጊስ የዲክታተር ጉዞ መቆሚያው የት ላይ ሊሆን ነው ? የሚል ጥያቄ በማቅረብ፤ መላው የንጉሣውያን ቤተሰብ ሥጋታቸውንና አንድነታቸውን በማስተባበር በንጉሠ ነገሥቱ ላይ ከፍ ያለ ተፅዕኖ አደረጉ።

ወልደጊዮርጊስ ደግሞ በበኩላቸው፤ በንጉሠ ነገሥቱና በራሳቸውም ሙሉ ዕምነት ስለአደረባቸው፤ የንጉሣውያን ቤተሰብን መልካም አስተያየት ለማግኘት ጊዜዬን ማባከን የለብኝም አሉ። በዚህም አኳኋን የሚወስዷቸው አንዳንዶቹ እርምጃዎች ጠቡን የሚያጋግሉ እንጂ፤ የሚያበርዱ አልሆኑም። ለምሳሌም ያህል፡-

- አልጋወራሽ አስፋወሰን የወሎ ግዛታቸውን በአስተዳደር ምን ያህል እንደበደሉት፤
- ልዑል መኰንን በሐረር መስፍንነታቸው ለሕዝቡ አንዳች ጠቃሚ ነገር እንደማይሠሩ፤

ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ በይፋ ባይናገሩትም፤ ከሥራ ረዳቶቻቸው ጋር ምን ይሻላል? ... እያሉ መወያየታቸው የተደበቀ ምሥጢር አልሆነም። ስለዚህም፤ ልዑል መርዕድ አዝማች አስፋወሰንና ልዑል መኰንን፤

1ኛ/ በተሰጣቸው በወሎና በሐረር ጠቅላይ ግዛቶች ከወረዳ እስከ አውራጃ ገዥነት በቀጥታ የሚሰጡት ሹመት እንዲቀርና፤ ጉዳዩ በሚመለከተው በአገር ግዛት ሚኒስትሩ ተጠንቶ ሲቀርብ፤ በንጉሠ ነገሥቱ የሚጸድቅ ሹመት መሆን እንደሚገባው፣

2ኛ/ ለእነዚህ ለሁለቱ ጠቅላይ ግዛቶች ለእያንዳንዳቸው የተወሰነላቸውን የዓመት የሥራ ማስኬጃ በጀት፤ የሚያዙበትና የሚያስተዳድሩት፤ በንጉሠ ነገሥቱ የተሾሙት እንደራሴዎች እንጂ፤ በልዑላኖቹ መስፍኖች መሆን እንደሌለበት፣

ወልደጊዮርጊስ ፕላን ነድፈው ለማስወሰን መዘጋጀታቸው እንደተሰማ፤ ሁለቱ ልዑላን ወንድማማቾች እጅግ ከፍ ያለ ብስጭት አደረባቸው። በተጨማሪም ወልደጊዮርጊስ ይህንን ያቀዱት፤ ንጉሣውያን ቤተሰብን ከመንግሥት ተግባር ለማራቅ ብቻ ሳይሆን፤ ሆነ ብለው ለማጥቃት ያሰቡበት ተንኮል ነው ተብሎ ተተረጐመ። ወልደጊዮርጊስ ግን በጃንሆይ ለማስወሰን ላቀዱት ሐሳብ ምክንያት የሰጡት፤ በሁለቱ ልዑላኖች የበላይ ገዥነት የሚተዳደሩት የወሎና የሐረር ነዋሪዎች በፍርድና በአስተዳደር ተበድለናል በማለት የሚያቀርቡትን አቤቱታ በማየት፤ የንጉሠ ነገሥታችንን ልጆች ነፃ ለማድረግ ነው የሚል ነበር። እንግዲህ! ስለ ወልደጊዮርጊስ ፕላን ቀናው አስተያየት ይህ ከዚህ በላይ የተሰጠው ምክንያት ሲሆን፤ በሌላ አነጋገር እውነተኛው የእጅሬ ዓላማ፤ ልዑላኖቹ በዓመት ሁለት ጊዜ ወደየግዛታቸው እየሄዱ፤ ሕዝቡን በመጐብኘትና ግብር በማብላት፤ የመስፍንነት ተግባራቸውን ይፈጽሙ እንጂ፤ በአስተዳደሩ ውስጥ እንዳይገቡ ለማድረግ ነው።

ይህንን ሐሳብ ጸሐፊ ትዕዛዝ በማስታወሻ እንዲዘጋጅ አደረጉ እንጂ፤ የሚመቻቸውን ጊዜ በመጠበቅ ለጃንሆይ አላቀረቡትም ነበር። የጽሕፈት ሚኒስትሩ ታማኞቼ ናቸው ብለው ካቀረቧቸው ጸሐፊዎች መካከል፤ አንዳንዶቹ ለጥቅም በመገዛት ወልደጊዮርጊስ በምሥጢር የሚያዘጋጁትን ቅጅ እያደረጉ ለሚያስፈልገው ወገን ስለሚሰጡ፤ ይህንን የልዑላኖቹን ግዛቶች ፕላን ጉዳይ በመጀመሪያ ያገኙት ልዑል መኰንን ናቸው ይባላል። በዚህ በጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ጉዳይ መንፈሳዊቷ ንግሥት እቴጌ መነንም የሚወራውን ሁሉ እየሰሙ ዝም ማለት አልቻሉም። የሚመስላቸውን ሐሳብ ሳያመነቱ ተናግረዋል። " .... መቸም ይኸ ሰው ጠባዩ ተለውጦ በጣም ትልቅ ነኝ እስከ ማለት ደርሷል የሚባለውን ሁሉ ጆሮአችን ይሰማል። ልጆቻችንም አስፋወሰንና መኰንን ተከታትለው እንደደረሱበት፤ ሁለቱንም ከየግዛታቸው ለማስነሣትና እሱ በሚፈልጋቸው ሰዎች ለመተካት ማሰቡን ሰምተዋል። ለዚህም ምክንያቱ ምንድን ነው? ሲባል፤ ሁለቱም ለየግዛታቸው ምንም አይሠሩም። በዚሁ ምክንያት ከሕዝቡም ጋር አልተኳኋኑም የሚል መልስ ይሰጣል አሉ። ይኸ መቸም እውነት ከሆነ ትልቅ ድፍረት ነው። ዛሬ በልጆቻችን ላይ የተጀመረ ጥቃት፤ ነገ ወደማን ሊደርስ ነው? ብሎ ማሰብ ያስፈልጋል። ሰው መቸም የተቀበለውን አደራ ለውጦ በራሱ መንገድ መሄድ ሲጀምር፤ በጣም ዘልቆ እስኪያበላሸና ራሱም እስኪበላሽ ድረስ ከመጠበቅ፤ ማንንም ሊጐዳም ሊጠቅምም ወደማይችልበት ቦታ አዛውሮ መገላገል ነው። ይኸ ሲባል በዚያ በመከራው ዘመን ይኸ ሰው ጃንሆይን ሳይለይ እስከ ደስታችን ቀን ድረስ ያገለገለ ስለሆነ፤ ከነበረበት ሥራ የሚዛወረው ጉዳት እንዲያገኘው ሳይሆን፤ ሥልጣኑ እንዲቀነስ ነው። ስለዚህ ከቀለቡም ከመሶቡም መጓደል የለበትም .... "*

---

* ከእቴጌ ጸሐፊ ከበጅሮንድ ገብሩ ገብረማርያም የተገኘ

እንደሚታየው የግርማዊት እቴጌ ሐሳብ፤ ከሌሎቹ ንጉሣውያን ቤተሰብ አስተያየት ጋር የሚገጣጠም ሆነ። ልዑል ራስ ካሣ፤ ልዑላኖች አልጋወራሽና የሐረሩ መስፍን፤ የጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ የሥልጣን ይዞታ አሁን በሚያደርገው እርምጃ ከቀጠለ፤ መቆሚያው የት ላይ ነው? በማለት ንጉሠ ነገሥቱን ከማሳሰብ አላቋረጡም ነበር። አሁን ደግሞ የሕይወት ጓደኛቸው ግርማዊት እቴጌ ልጆቻቸው ባስረዷቸው መሠረት፤ የወልደጊዮርጊስን የሥራ ዝውውር አጥብቀው ሲደግፉ፤ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ችላ ማለት አልቻሉም። በዚህም መሠረት ለቤተሰቦቻቸው የሚከተለውን ሐሳብ ገለጹላቸው።

**" ... ወልደጊዮርጊስን በሥራ ችሎታውና በትጋቱ መርጠን አጠገባችን እንዲያገለግለን ካደረግነው፤ ሐያ ሦስት ዓመት ሆኗል። በዚህ ጊዜ ውስጥ ከታማኝነቱና ፍሬ ያለው አገልግሎት ከመስጠቱ በስተቀር እንከን አላገኘንበትም። እርግጥ! በሥራው ላይ አስተዋይና ብልህ፤ ጠንካራና ሐቀኛ ቢሆንም፤ ከብዙ ሰዎች ጋር ስለሚጋጭ ብዙ ጠላቶች አፍርቷል። ጠላቶች ቢበዙበትም በሥራው ድክመት አላሳየም። ገዥዎችም ሆኑ ሚኒስትሮች ለእኛ በሚያቀርቡት ራፖር፤ ማለፊያ የሠሩትን በእኛ ስም ሲያተጋቸው፤ የሰነፉትን ከወቀሳ አይምራቸውም። ይህን የመሰለውንም አሠራር እንዲቀጥል ዝም ብለን የተመለከትነው፤ ለአገር ዕድገት ጠቃሚነቱን እንጂ፤ ጉጂ ሆኖ ስላልታየን ነው። ሌላው ጠባዩ ሥልጣን ወዳድነቱ ነው። መውደድ ብቻ ሳይሆን በሥልጣን መጠቀምንም ያበዛዋል። ብዙ ጠላቶችም ያፈራው በዚሁ በሥልጣን አጠቃቀሙ እያየለባቸው ነው። የቅርብ ወዳጆቹ ነን የሚሉትም ቢሆኑ፤ በሥራው ላይ የሚያሳየውን ቁጥጥርና ኃይለኛነት አይደግፉትም። ከገዥዎችም፤ ከሚኒስትሮቹም አንዳንዶቹ ወደ እኛ ዘንድ እየቀረቡ የሚያመለክቱን፤ ኃይለኛነቱን ስለአበዛው እንዲቀንስና ከሰዎች ጋር መግባባትን እንዲፈጥር አስደርጉልን እያሉ ነው። ከዚህም በቀር የወልደጊዮርጊስ ምኞቱ "ጠቅላይ ሚኒስትር" ተብሎ ለመሾም ስለሆነ፤ ይኽ ምኞት ቢፈጸም ምን ያህል አደገኛ እንደሆነ ሥጋታቸውን ተናግረዋል። እኛም ራሳችን እንዳጠናነው ወልደጊዮርጊስ ጠቅላይ ሚኒስትር ለመሆን ምኞት እንዳለው ተሰምቶናል። ሆኖም በእኛ በኩል ለዚህ ቦታ እንመርጥሃለን ብለን የሰጠነው ተስፋ የለም።**

እንግዲህ! አሁን እናንተ እንዳያችሁት፤ የዚህ ሰው ጠባይ መለወጥና የሥልጣን ኃይል እየተሰማው መሄድ ያሳሰበው፤ የመንግሥታችን ኃላፊዎች የሆኑትን ዋና ዋና ሰዎች ብቻ ሳይሆን፤ በይበልጥ ደግሞ ቤተሰባችንን ጭምር መሆኑን ነው። አሁን እቴጌ የተናገረችው በጣም ታላቅ ነገር ነው። **"ዛሬ በልጆቻችን ላይ የተጀመረ ጥቃት፤ ነገ ወደ ማን ሊደርስ ነው? ብሎ ማሰብ ያስፈልጋል"** ብላ ጠይቃለች። ልጆቻችን አስፋወሰንና መኰንን እኛ ወደንና ፈቅደን በሰጠናቸው ግዛት፤ ለሕዝቡ አልሠሩለትም። በዚህም ምክንያት በቦታቸው ሌሎች ይተካሉ ብሎ ከወዳጆቹ ጋር መመካከሩና ማሰቡ እውነት ከሆነ፤ ከዚህ የበለጠ የሚያሳስብ ነገር የለም። በዚህ አኳኋን እቴጌ ላቀረበችው ጥያቄ መልሱ እንዲገኝለት ያስፈልጋል። ሁላችሁም እንደምታውቁት፤ **"ወሬ" በጣም መጥፎ በሽታ ነው። ከተከታተሉት ያጠፋል እንጂ፤ አይምርም። ስለዚህ፤ በወሬ የሚፈጸም ነገር ስለሌለ፤ ያለመሸበር አስፈላጊውን ጥንቃቄ እያዘጋጁ መጠበቅ ነው።**

እንግዲህ! ለዚህ ሁሉ መድኃኒቱና ማሠሪያው ምንድን ነው? .... እኛ እስካሁን እንዳየነው፤ ሚኒስትሮቻችንና የሕዝባችን አስተዳዳሪዎች አድርገን የሾምናቸው ገዥዎችም፤ የመንግሥታችን ባለሥልጣኖችና የጦር አለቆችም፤ በወልደጊዮርጊስ ሥልጣን ክፉኛ ሠግተዋል። ከነዚሁም አንዳንዶቹ እኛ በንጉሠ



ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ሁለቱን ልዑላን ልጆቻቸውን፤
ከግራ ወደ ቀኝ ልዑል አልጋወራሽ አስፋወሰንና
ልዑል መኰንን መሥፍነ ሐረርን ሲያነጋግሩ፤

ነገሥትነታችን ለስሙ ያህል በጽሕፈት ጠረጴዛችን ላይ እንገኛለን እንጂ፣ የመንግሥቱን ሥራዎች የሚያንቀሳቅሰውና የሚወስነው ወልደጊዮርጊስ ነው ብለው እስከማመን ደርሰዋል። እኛ ግን እስከዛሬ ድረስ ይህንን ሁሉ እየሰማን በትዕግሥት በማሳለፍ የቆየነው፣ መኸመሪያ ብዙ ስለምንሠራና የሥራዎቻችንን ውጤቶች ለማየት ስለጓጓን፣ ሁለተኛ ጠንካራ ሠራተኛችን የሆነውን ወልደጊዮርጊስን፣ በአንዳንድ ፍሬቢስ በሆኑ ወሬዎች ተመርተን በምንወስድበት እርምጃ መንፈሱ እንዳይደክም በማሰብ ነበር። ነገር ግን ይህ በቅን መንፈስ ስንመለከተውና በትዕግሥት ስናሳልፈው የቆየነው ጉዳይ፣ እያደር ሌላ ነገር እየጨመረና እየገነነ በመንዝዝ አደገኛ የመሆን አቅጣጫ የያዘ መሰሏል። ለዚህም፣ በቤተሰባችንና በሥራ ረዳቶቻችን አስተያየት፣ መድኃኒቱ ወልደጊዮርጊስን አሁን ካለበት ሥራ ወደ ሌላ ቦታ ማዛወር ነው ስለተባለ፣ እኛም ፈቃዳችን ሆኖ ለመፈጸም አንቸገርም። ነገር ግን ይህንን ሐሳብ በአሁኑ ሰዓት በቶሎ ለማድረግ የሚያውከን አንድ ትልቅ ጉዳይ አለ። ይኸውም፣ ሁላችሁም እንደምታውቁት፣ የዩናይትድ ስቴትስ አሜሪካና የታላቋ ብሪታኒያ መንግሥታት እንዲሁም ዋና ዋናዎቹ የአውሮፓ መንግሥታት አገሮቻቸውን እንድንጉበኝላቸው ያቀረቡልንን የክብር ጥሪ ተቀብለን በመዘጋጀት ላይ ነን። ለዚህ ሁሉ ጉዞአችን ከየመንግሥታቱ እንደራሴዎች ጋር በቀጥታ እየተነጋገረ የሚያዘጋጀው የጽሕፈት ሚኒስትራችን ነው። እንግዲህ እንደምታዩት በዚህ ሁሉ ሥራ ማህል አቋርጠን ሹም ሽር ብናደርግ፣ የታሰበውን ጉዞ በደህና አኳኋን ለመፈጸም ያስቸግራል። ስለዚህ፣ የታቀደው የጉዞአችን ፕሮግራም እስኪጠናቀቅ ድረስ፣ ጉዳዩ በብርቱ ምሥጢር ተይዞ እንዲቆይ ያስፈልጋል። በዚሁም ጊዜ ውስጥ እኛም ራሳችን ሁኔታውን በቅርብ ለመከታተልና የበለጠ ለመረዳት እንችላለን" ካሉ በኋላ፣ እናንተስ ምን ታስባላችሁ? ብለው ሲጠይቁ ልዑል ራስ ካሣ የተናገሩት የሁሉንም ንጉሣውያን ቤተሰብ አስተያየት የሚያጠቃልል ሆነ።

" .... መቸም በታሪክም በልማድም እንደሚታወቀው፣ አንዳንድ ጊዜ ንጉሥ ያላየውንና ያልሰማውን፣ እያዩና እየሰሙ ክፉና ደጉን እየለዩ፣ ለንጉሥ ውሳኔ የሚያቀርቡት ቤተሰቦችና ታማኝ አገልጋይዎች ናቸው። በዚህም አኳኋን በሚወዱት ሚኒስትርዎ በጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ጉዳይ፣ ቤተሰቦችዎም፣ ዋና ዋና ታማኝ አገልጋይዎችዎም፣ የሰውየውን አደገኛነት በማየት፣ አሁን ካለበት ሥራ ተነሥቶ ወደ ሌላ ጉዳት ወደማያስከትል ቦታ ቢዛወር ይሻላል ተብሎ ሐሳቡ ቀርቦልዎታል። ጃንሆይም ይህ ጉዳይ አሳሳቢ መሆኑን አይተው ጉዳዩን ለአንዴም ለመጨረሻም ለመገላገል የሚቻለው፣ የቀረበልዎትን ሐሳብ በመፈጸም ብቻ መሆኑን ተቀብለውታል። ነገር ግን ጉዳዩን ዛሬና ነገ ሳይባል በቶሎ ለማከናወን፣ በጃንሆይ ላይ ችግር የፈጠረው ይኸ የአሜሪካኖቹና የእንግሊዞቹ አገር መጉብኘት ጉዳይ ነው። ይኸ ከታላላቆቹ ነገሥታቶች የቀረበልዎት ጥሪ የአገር ጥቅም ስለሆነ፣ በደህና አኳኋን መከናወን አለበት። ይህንንም ትልቅ ጉዞ የሚያዘጋጀው ይኸው እሱ ሳይሰማና ሳያውቅ በጀርባ የምንመክርበት ሰው ከሆነ፣ እሱ የጀመረውን እሱ ይጨርስ ከማለት በስተቀር ሌላ ምን ማድረግ ይቻላል? ... መቸም ጃንሆይ በሚሄዱበት ሁሉ እሱንም ይዘውት ስለሚሄዱ፣ እዚህ ቀርቶ ተንኮል ለመጉንጉን ይመቸዋል ብለን አናስብም። ስለዚህ፣ ከጉዞዎ በደህና ወደ አገርዎ እንደተመለሱ የታሰበውን ፈጣሪያችን እንዲያስፈጽምልዎ ሁላችንም በጸሎት እንደክማለን። .... "

ጃንሆይ በራስ ካሣ አስተያየት በጣም ተደሰቱ። የአሜሪካና የአውሮፓ አገሮች ጉብኝት እስከሚፈጸምበት ጊዜ ድረስ፣ የአጅሬ የወልደጊዮርጊስ ጉዳይ፣ በብርቱ ምሥጢር ተይዞ እንዲቆይ ተወሰነ።

# ምዕራፍ ፲

## ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ በአሜሪካ ጉዞ ላይ

ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ በኢትዮጵያ ነገሥታት ታሪክ ለመጀመሪያ ጊዜ ተብሎ የሚመዘገበውን፤ የዩናይትድ ስቴትስንና የአውሮፓን አገሮች በኦፊሲየል ለመጐብኘት ሲወስኑ፤ ለጠቅላላው ዝግጅት ሙሉ ኃላፊነት የወሰዱት የጽሕፈትና የፍርድ ሚኒስትሩ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ነበሩ።

ይህም ኃላፊነት፤ ንጉሠ ነገሥቱ ከመናገሻ ከተማቸው ተነሥተው በየአገሩ የሚጓዙበትንና የሚያደርጉትንም ጉብኝት ብቻ ሳይሆን፤ ጃንሆይ ከአገር ውጭ በሚቆዩባቸው ጊዜያቶች ኢትዮጵያን በተጠባባቂነት የሚመሯት የአልጋወራሹ የሥልጣን ኃላፊነት፤ እስከምን ድረስ መሆን እንደሚገባው ማዘጋጀት ነበር።

ጸሐፊ ትዕዛዝ፤ ቢያንስ በሳምንት ሦስት ጊዜ ውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር እየተመላለሱ፤ ጉዳዩ ከሚመለከታቸው ባለሥልጣኖች ጋር ስብሰባ በማድረግ፣ አዲስ አበባ ያለውን የአሜሪካንን አምባሳደር እየጠሩ በማነጋገር፣ ዋሽንግተን ካሉት ከኢትዮጵያ አምባሳደር ካቶ ይልማ ዴሬሣ ጋር በኮድ መልዕክት በመለዋወጥ፤ የንጉሣዊውን ረዥም ጉዞና ጉብኝት ሲያዘጋጁ ብዙ ቀናት አሳልፈዋል። ይህንን የመሰለው የጉብኝት ዝግጅት ከዚህ ቀደም ያልተደረገና ልምዱም ስላልነበረ፤ የእያንዳንዱ አገር የመስተንግዶ ወግና ሥርዓት ንጉሠ ነገሥቱን በሚያስደስት መልክ እንዲሆን ለማድረግ፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ ምን ያህል እንደደከሙበት በዚያን ዘመን ውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር ይሠሩ የነበሩት ሰዎች ሁሉ ተናግረዋል።

በዚህ አኳኋን የንጉሠ ነገሥቱ የአሜሪካ ጉብኝት አስፈላጊው ዝግጅት በሚጠናቀቅበት ጊዜ፤ ከዋሽንግተን የስቴት ዲፓርትመንት ባወጣው ረቂቅ ፕሮግራም ላይ፤ ጃንሆይ ዋሽንግተን ሲደርሱ በአውሮፕላን ጣቢያ ተገኝቶ የሚቀበላቸው ምክትል ፕሬዚዳንቱ ሪቻርድ ኒክሰን ነው እንጂ፤ ራሱ ፕሬዚዳንት አይዘንሐወር አለመሆኑ ሲታወቅ፤ በአዲስ አበባ ከፍ ያለ ድንጋጤ ተፈጠረ። ወዲያው ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ በዋሽንግተን ለኢትዮጵያ አምባሳደር ለክቡር አቶ ይልማ ዴሬሣ ባስተላለፉት ቴሌግራም፤ « .... አንተን የሚያህል ትልቅ አምባሳደር በተመደበበት አገር፤ ንጉሠ ነገሥታችንን እና ኢትዮጵያን የሚያዋርድ የአቀባበል ፕሮግራም መዘጋጀቱ እጅግ የሚያሳዝን ሆኗል። አሁንም የንጉሠ ነገሥቱንና የኢትዮጵያን ክብር በማሰብ፤ ይህንን አዋራጅ የሆነ የአቀባበል ፕሮግራም ለማስለወጥ፤ ብርቱ ጥረት እንድታደርግ ጥብቅ አደራዬን እልክልሃለሁ። ጃንሆይ ቢሰሙ፤ ምን ያህል እንደሚያዝኑ ስለምናውቅ እስካሁን አልነገርናቸውም .... » የሚል ቃል ተጠቀሙ። በዚያን ጊዜ በዋሽንግተን የኢትዮጵያ ኤምባሲ አማካሪ የነበሩት ዲፕሎማት አቶ አድመው ተሰማ በሮም አምባሳደር በነበሩበት ጊዜ በ1957 ዓ.ም እንዳጫወቱኝ፤ አቶ ይልማ ይህ የወልደጊዮርጊስ አስደንጋጭ ቴሌግራም ሲደርሳቸው፤ መበሳጨታቸውን ሆነ ማዘናቸውን ማሳየት አልፈለጉም። መልሱ ሳይዘገይ ለጃንሆይና ለጸሐፊ ትዕዛዝ

እንዲላክ አደረጉ። « ... ፕሬዚዳንት አይዘንሐወር የአሜሪካ መሪ ሆነው ከተመረጡበት ጊዜ አንሥቶ የዋይት ሐውስ ቤተመንግሥት ባወጣው የፕሮቶኮል ደንብ፤ የአንድ የውጭ አገር መሪ ለኦፊሲየል ጉብኝት ዋሽንግተን በሚመጣበት ጊዜ፤ በአውሮፕላን ማረፊያ ተገኝቶ እንኳን ደህና መጣህ የሚለው ምክትል ፕሬዚዳንቱ ነው። ፕሬዚዳንቱ እንግዳውን መሪ የሚቀበሉት፤ በዋይት ሐውስ መግቢያ በር ላይ ሆነው ነው። ስለዚህ፤ ለግርማዊ ንጉሠ ነገሥት ጉብኝት የተዘጋጀው ፕሮግራም እስከዛሬ ድረስ ለሌሎች መሪዎች ከተደረገው የተለየ አይደለም። **እኔም የግርማዊነታቸው አምባሳደር የዋይት ሐውስን ፕሮቶኮል ለማስለወጥ የማልችል፤ ሙከራም የማላደርግ መሆኔን በትሕትና እገልጻለሁ። .. »** ሲሉ በጠንከረ ቃል መልዕክታቸውን አስተላለፉ። ጸሐፊ ትእዛዝ ዝምታን መረጡ።

ጃንሆይ ግን ሳይውል ሳያድር፤ በሰጡት መልስ፤ « .... **በዋሽንግተን ለመሪዎች አቀባበል ከሚሠራበት ደንብ ውጭ፤ ለእኛ የተለየ ነገር እንዲደረግልን እኛም የማንፈቅድ መሆኑን እንድታውቀው ይሁን።** ..... » አሉ። ከዚህ በኋላ ይህ የአሜሪካ የጉብኝት ፕሮግራም በዝርዝር በሚዘጋጅበት ጊዜ፤ የንጉሠ ነገሥቱ ዋና ዋና የክብር ተከታዮች ቁጥራቸው ከዐሥር እንዳይበልጥ አሜሪካኖቹ በጠየቁት መሠረት፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ከጃንሆይ ጋር ተነጋግረው የሚከተሉት ሰዎች ተመረጡ።

**ሀ/ ከንጉሣዊ ቤተሰብ፤**

1. ልዑል ሣህለሥላሴ (የጃንሆይ ልጅ)፣
2. እመቤት ሰብለ ደስታ (ኂላ ልዕልት) የጃንሆይ የልጅ ልጅ፣

**ለ/ ከመንግሥት ባለሥልጣኖች፤**

3. ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ የጽሕፈትና የፍርድ ሚኒስትር፣
4. አቶ አክሊሉ ሀብተወልድ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር፣
5. አቶ ተፈራወርቅ ኪዳነወልድ የጃንሆይ ልዩ ጸሐፊ፣
6. አቶ ይልማ ዴሬሣ በዋሽንግተን የኢትዮጵያ አምባሳደር፣
7. ኮሎኔል መኰንን ደነቀ ዋና የእልፍኝ አስከልካይ፣
8. ልጅ እንዳልካቸው መኰንን የፕሮቶኮል ሹም፣

የእነዚህ የክብር ተከታዮች ስም ዝርዝር ለአሜሪካን አምባሳደር ከተላለፈ በኋላ፤ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ አንድ ሐሳብ አደረባቸው። ይኸውም ከአሜሪካን መንግሥት የጦር መሣሪያ ዕርዳታ ለማግኘት እንደምንጠይቅ ስለተወሰነ፤ ጉዳዩ የሚመለከታቸው የጦር ሚኒስትሩ ብሪጋድየር ዤኔራል ዓቢይ አበበ ከተከታዮቹ ውስጥ እንዲመደቡ ያስፈልጋል፤ በማለት አክሊሉ ሀብተወልድ ያቀረቡትን ሐሳብ ንጉሠ ነገሥቱ ወዲያውኑ ፈቀዱ። **የዤኔራል ዓቢይ ከክብር ተከታዮች ውስጥ መመደብ የትልቁን ባለሥልጣን የወልደጊዮርጊስን የፕሮቶኮል ደረጃ ዝቅ እንደሚያደርገው፤ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ አላሰቡበትም።** ከዚህም በላይ የጉዞው ዝግጅት ዋና ኃላፊ የሆኑትን ጸሐፊ ትዕዛዝን ሳያማክሩ ጉዳዩን በቀጥታ ለጃንሆይ አቅርበው ማስወሰናቸው፤ የጽሕፈት ሚኒስትሩን ቅር እንደሚያሰኝ አልታያቸውም።

በመሠረቱ የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት ፕሮቶኮል ለብዙዎቹ አገሮች ትርጉሙ በትክክል የማይታወቅና በአንዳንድ ረገድም እጅግ አስገራሚ ሆኖ የኖረ ነው። ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ በዕድሜና በአገልግሎት፣ በካቢኔ ሚኒስትርነትና



ለመጀመሪያ ጊዜ የአሜሪካ መንግሥት እንግዳ በመሆን፤
ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ለጉብኝት ዋሽንግተን ሲደርሱ፤

በሥልጣን ከጄኔራል ዓቢይ አበበ ምንያህል እንደሚበልጡ ለማንም ግልጽ ነው። ለምሳሌም ያህል፤ ዓቢይ አበበ ሙሉ የጦር ሚኒስትር ሆነው የተሾሙት (ጥቅምት 26/1944) ወልደጊዮርጊስ ጸሐፊ ትዕዛዝ ተብለው የጽሕፈት ሚኒስትር ከሆኑ ከዐሥራ አንድ ዓመት በኋላ ነው። ነገር ግን ዓቢይ አበበ በሚያዝያ 18 ቀን 1934 ዓ.ም፤ የንጉሠ ነገሥቱን ልጅ ልዕልት ፀሐይ ኃይለሥላሴን በሕግ አግብተው "አማች" ሲሆኑ፤ በቤተመንግሥቱ የተሰጣቸው የፕሮቶኮል ወንበር፤ ከካቢኔ ሚኒስትሮች ብቻ ሳይሆን ከትልቁ ባለሥልጣን ከጸሐፊ ትዕዛዙ በላይ ሆነ። ጄኔራል ዓቢይ ከልዕልት ፀሐይ ጋር ጋብቻቸውን በፈጸሙ በጥቂት ወራት ውስጥ፤ በድንገተኛ ሕመም ባለቤታቸው ከሞቱባቸው በኋላ ሌላ ትዳር ቢይዙም፤ ያው የቀድሞው የፕሮቶኮል ደረጃቸው እስከ ሺህ ዘጠኝ መቶ ሃምሳ ስምንት ዓ.ም /1958/ ድረስ ሳይለወጥ ተጠብቆ ቆየ።

ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ የዚህን የአሜሪካኑን ጉዞ ሲያዘጋጁ፤ ከንጉሠ ነገሥቱ ቀጥሎ እንደ ጠቅላይ ሚኒስትር የሚቆጠሩት ትልቁ ባለሥልጣን ራሳቸው ስለሆኑ፤ በኤኮኖሚ ልማት ሆነ በጦር መሣሪያ ረገድ ወዳጆቻችን አሜሪካኖች፤ የሚበቃ እርዳታ እንዲሰጡን በቀጥታ ለመነጋገር የጋለ ምኞትና ዕቅድ ነበራቸው። ነገር ግን የጦር ሚኒስትሩ የክብር ተከታይ ሲሆኑ፤ ደረጃቸውን ከሁለተኛነት ወደ ሦስተኛነት ስለሚያዛውረው፤ የማስበውን ሁሉ ለመፈጸም ያዳግተኛል በማለት ቅሬታ ተሰማቸው። ይህም ቅሬታ ፕሮቶኮሉ በፈጠረው ችግር እንጂ፤ በልዩ ወዳጃቸው በጄኔራል ዓቢይ ላይ እንዳልሆነ የታወቀ ነበር። የጸሐፊ ትዕዛዝ ትክክለኛው ሐሳብ፤ የጦር መሣሪያ እርዳታ ለመጠየቅ ከአሜሪካ ባለሥልጣኖች ጋር ንግግር በሚደረግበት ጊዜ፤ መሣሪያዎቹንና ዓይነታቸውን ለማስረዳት የሚችል፤ አንድ ከፍተኛ የጦር መኰንን ይዞ መሄድ ሲቻል፤ ለዚህ ጉዳይ ተብሎ የጦር ሚኒስትሩን የክብር ተከታይ ማድረግ አስፈላጊ አልነበረም፤ የሚል ነው። ለማናቸውም፤ አንድ ጊዜ በንጉሠ ነገሥቱ የተወሰነውን ለማስለወጥ መሞከሩ ሌላ ጣጣ ስለሚቀሰቅስ፤ በዚሁ ይቀጥል ተባለ።

ይህ ከዚህ በላይ የተገለጸው በምን አኳኋን ሊደርስ እንደቻለ፤ አክሊሉ ሀብተወልድ የሚከተለውን ነግረውኛል። ይህን ጉዳይ የጽሕፈት ሚኒስትሩ በሌሉበት፤ ለጃንሆይ አቅርቤ በአስቸኳይ ያስወሰንኩት፤ በዚያን ጊዜ ጸሐፊ ትዕዛዝ ጉንፋን አሟቸው ወደ ቢሾፍቱ በመሄዳቸው ነበር። ከዚህም በቀር ሐሳቡን እሳቸው የሚደግፉት እንጂ ቅር የሚሰኙበት መሆኑን አልገመትኩም። በእኔ ላይ ቅር መሰኘታቸውን ካየሁ በኋላ፤ ምክንያቱን ዘርዝሬ ላስረዳቸው ብሞክር፤ ለማዳመጥ አለመፈለጋቸውን አሰሙኝ። ቢቸግረኝ፤ ወንድሞቼን አቶ መኰንንን፣ አካለወርቅና መክብብን አማከርኳቸው። አቶ መኰንን እንዲህ አለኝ። «... በችኰላ ባስወሰንከው ጉዳይ ጸሐፊ ትዕዛዝ ቅር ቢሰኝ ሊያስገርምህ አይገባም። ታሞ ቢሾፍቱም ቢሆን በስልክ ብታነጋግረው ይሆን ነበር። አሁን የሚሻለው፤ ዝርዝር ክርክር ውስጥ ሳትገባ ስሕተት መስሉ ለታየው ጉዳይ በደፈናው ይቅርታ ለምነው። ጸሐፊ ትዕዛዝ ባንተ ስለማይጨክን ይቅርታ አይነፍግህም። .... » አለኝ። በአቶ መኰንን ሐሳብ አካለወርቅ ሲስማማ፤ መክብብ እንደተለመደው አፈነገጠ። " ይቅርታ የሚያስጠይቅ ነገር የለም " ብሎ አከረረ። ከዚያም ቀጠለና፤ « ... እናንተ እኮ አልገባችሁም። የጸሐፊ ትዕዛዝ ዘመን አልቋል። ሕዝብ ተነሥቶባቸዋል። አምላክ ተጣልቷቸዋል። ጃንሆይም ከእሳቸው ለመገላገል እሳቱን አዳፍነው ይጠብቋቸዋል። ስለዚህ ቀናቸው ስለደረሰ እሳቸውን መለማመጥ ለምን አታቆሙም ? .... » አለ። አቶ መኰንን ወዲያው መለሰለት « ... ታዲያ ለተዳፈነው እሳት አቀጣጣይ ለመሆን ከአንተ የተሻለ የኤሌክትሪክ መሐንዲስ የት ይገኛል ? ለምን ዕጩ ሆነህ

አትቀርብም ? ... » አለው። በዚህ ጊዜ ሁላችንም በሳቅ ሞትን። ወንድማችን መክብብ፤ ሁልጊዜ የሚያስበውን እንደልቡ ስለሚናገር፤ በተሰበሰብን ቁጥር ሳንስቅ እንለያይም ነበር። በመጨረሻው አቶ መኰንን የሰጡኝን ምክር ተከትዬ፤ ስለደረሰው ጉዳይ ዝርዝር ውስጥ ሳልገባ ይቅርታ ያድርጉልኝ ብዬ ለመንኳቸው። እሳቸውም ጊዜ ሳይወስዱ ይቅርታውን ተቀብለው ሳሙኝ። እኔም ሰላም አገኘሁ ብዬ ስደሰት ሌላ አዲስ ነገር ተፈጠረ። የደረሰው ችግር የሚከተለው ነበር።

ጆዜፍ ሳይመንሰን (Joseph Simonson) በአዲስ አበባ የአሜሪካን አምባሳደር የንጉሠ ነገሥቱን የክብር ተከታዮች ዝርዝርና ቅደም ተከተላቸውን ወደ ዋሽንግተን ባስተላለፈ ጊዜ፤ በዚያ ያለው የስቴት ዲፓርትመንት ፕሮቶኮል ሹም የኢትዮጵያን ቤተመንግሥት ወግና ሥርዓት አልቀበልም ብሎ ለዋወጠው። በአሜሪካ የፕሮቶኮል ሹም አስተያየት፤ የጃንሆይ ልጅና የልጅ ልጅ የሆኑት ልዑል ሣህለሥላሴና ልዕልት ሰብለ ደስታ ልዩ የክብር እንግዶች ስለሆኑ፤ የተለየ ፕሮቶኮል ይደረግላቸዋል። የጃንሆይ ተከታዮች ሆነው ከሚመጡት ባለሥልጣኖች መካከል፤ ከንጉሠ ነገሥቱ ቀጥሎ የፕሮቶኮል ወንበር የሚሰጠው፤ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ ስለሆነ፤ ለሌሎቹ ለጦርና ለጽሕፈት ሚኒስትሮቹ ከአዲስ አበባ በተላለፈው መሠረት ቅደም ተከተላቸው ይፈጸማል ብሎ ወሰነ።

ጸሐፌ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ በገኔራል ዓቢይ ምክንያት ፕሮቶኮሉ ከንጉሠ ነገሥቱ በኋላ ሁለተኛ ሰው ስለአደረጋቸው ሲገረሙ፤ አሁን ደግሞ ወደ ሦስተኛ ደረጃ ለማዛወር የሚታሰብላቸው ሆነው ተገኙ። በአዲስ አበባ እኔ ከአሜሪካን አምባሳደር ጋር በዋሽንግተን የኢትዮጵያ አምባሳደር አቶ ይልማ ዴሬሣ ከስቴት ዲፓርትመንት ጋር የታሰበውን ለማስለወጥ ስንከራከር፤ የአሜሪካን የፕሮቶኮል ሹም የባሰ ይባስ ብሎ፤ በአሜሪካ ወግና ሥርዓት ከንጉሠ ነገሥቱ ቀጥሎ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር አክሊሉ ሲሆኑ፤ ከእሳቸው ደግሞ የሚከተሉት አምባሳደር ይልማ ዴሬሣ ናቸው። ሌሎቹን ሚኒስትሮች ከእነዚህ ከሁለቱ ሰዎች በኋላ እንደፈለጋችሁ ደልድላችሁ ማቅረብ ትችላላችሁ ሲል የቀድሞ ሐሳቡን ለውጦ አቀረበ። እዚህ ላይ ይልማ ዴሬሣ ኃይለኛ የሆነ ተቃውሞ አደረገ። " .... የንጉሠ ነገሥቱ የክብር ተከታዮች ከሆኑት የካቢኔ ሚኒስትሮች መካከል ለሥራ ይጠቅመናል በማለት፤ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ የመጀመሪያውን ቦታ እንዲይዙ የጠየቃችሁትን ቅር እያለን እንቀበለው ይሆናል። ነገር ግን ለእኔ ለአምባሳደሩ ከጦርና ከፍርድ ሚኒስትሩ በላይ የፕሮቶኮል ቦታ ለመስጠት ያቀዳችሁትን አንቀበለውም። .... " ሲል ይልማ ዴሬሣ የሰጠውን መልስ የፕሮቶኮል ሹሙ ተቀብሎ መስማማቱን አስታወቀ።

ይህን በዋሽንግተን የደረሰውን የፕሮቶኮል ችግር ጃንሆይ ሊያውቁት ይገባል በማለት፤ አቶ ይልማ የሚከተለውን የኮድ መልዕክት ለገነተ ልዑል ቤተመንግሥት አስተላለፈ። « .... ግርማዊነትዎ በአሜሪካ የሚፈጽመውን የኦፊሲየል ጉብኝት ፕሮግራም በምናጠናቅቅበት ሰዓት፤ በፕሮቶኮል በኩል የገጠመኝን ችግር ጃንሆይ ሊያውቁት የተገባ መስሎ ታይቶኛል። የግርማዊነትዎ የክብር ተከታዮች የሆኑትን የታላላቆቹን ሚኒስትሮች ስም ዝርዝርና የፕሮቶኮላቸውን ደረጃ ለስቴት ዲፓርትመንት ስናቀርብላቸው፤ ለውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ ከጦርና ከጽሕፈት ሚኒስትሮቹ በላይ የፕሮቶኮል ወንበር መስጠት አለብን ብለው አስቸግረውናል። በእኔ በኩል አሜሪካኖቹ የአገራችንን ፕሮቶኮል ቅደም ተከተል ሊያከብሩልን ይገባል በማለት መከራከሬን ባላቋርጥም፤ እስካሁን ውጤት አላገኘሁም። .... »

አገልጋይዎ ይልማ ዴሬሣ

የአምባሳደር ይልማ ዴሬሣ መልዕክት እንደደረሳቸው ንጉሠ ነገሥቱ መልሱን በፍጥነት ሰጡ።

ክግርማዊ ጃንሆይ፤
ይድረስ ላቶ ይልማ ዴሬሣ፤

« .... የክብር ተከታዮቻችን እንዲሆኑ በመረጥናቸው ሚኒስትሮቻችን መካከል የአሜሪካ ፕሮቶኮል የኛን ልማድ ባለመከተሉ፤ መቸገርህን በመግለጥ የላከው መልዕክት ደርሶናል። እኛ የዩናይትድ ስቴትስ መንግሥት የክብር እንግዶች ሆነን አገራቸውን በምንጐበኝበት ሰዓት፤ ለሚደረግልን አቀባበልና መስተንግዶ ኃላፊዎቹ እነሱ ስለሆኑ፤ የፕሮቶኮሉንም ጉዳይ ለእነሱ መተው ነው። ..... »

ይህ የጃንሆይ ውሳኔ ለችግሩ መፍትሔ የሰጠ መሆኑ ባይካድም፤ የአሜሪካ ፕሮቶኮል ባጠቃቸው በጦርና በጽሕፈት ሚኒስትሮቹ ላይ ያሳደረውን ቅሬታ የሚሰርዝ አልነበረም።

« .... ዋሽንግተን ከደረስን በኋላ ደግሞ፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስን የሚያስቆጣ ሌላ ችግር ብቅ አለ። ይኸውም፤ ጃንሆይ ስለ አገሮቻችን ግንኙነት ጉዳይ በዋይት ሐውስ ከፕሬዚዳንት አይዘንሐወር ጋር በሚነጋገሩበት ጊዜ፤ ተካፋዮቹ እኔና ይልማ ዴሬሣ ብቻ እንድንሆን በአሜሪካኖቹ በኩል የተወሰነውን ሲያውቁ ነው። ይህ የደረሰው በአክሊሉና በይልማ ግዴለሽነት ነው፤ የሚል ስሜት አደረባቸው። በፌዝ አነጋገር፤ ስማ አቶ አክሊሉ ! ለጃንሆይ መንግሥትና ለአገራችን ጉዳይ ትልልቆቹ ኃላፊዎች አንተና ይልማ ብቻ ከሆናችሁ፤ የእኔና የጄኔራል ዓቢይ መምጣት እንዲሁ (ለዴኮራሲዮን) ለጌጥ ኖርዋል ወይ ? አሉኝ። ለዚህ መልስ ሳልሰጥ ወዲያው ቀጠሉና ለመሆኑ የጦር ሚኒስትሩ ጃንሆይን መከተል አለበት ብለህ እንደዚያ በችኮላ ያስወሰንከው፤ አንተና ይልማ ትልልቁን ሥራ ስታከናውኑ፤ እኔ ብቻዬን ወንበር ላይ ሳንቀላፋ እንዳልውል ጓደኛ እንዲኖረኝ አስበህ ኖርዋል ወይ? አሉኝ። እኔ እንደሳቸው ሰውን በንግግር ማቁሰል ስለማላውቅበት መከራከሩን አልፈለግኩም። ባጭሩ፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ ! በዚህ በአሜሪካኖቹ ዝግጅት ማዘንዎ ትክክል ነው። ጥቂት ቢታገሡኝ መልሱን አመጣልዎታለሁ፤ ብዬአቸው ከነበርንበት ከብሌር-ሐውስ "Blair House" ሳሎን ወደ ውጭ ወጣሁ። እንደአጋጣሚ ከበሩ ላይ የስቴት ዲፓርትመንት የአፍሪካ ክፍል ዲሬክተር የሆነው ሚስተር ኡተር (Utter) እኔን ለማነጋገር ሲመጣ አገኘሁት። የመጣው ጃንሆይ ከአይዘንሐወር ጋር ስለሚነጋገሩበት ጉዳይ አጀንዳውን ለማስተካከል ነበር። ከሁሉ በፊት እኔ በጣም የሚያስቸኩል ትልቅ ጉዳይ ስለአለኝ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩን ሚስተር ደለስን ለአንድ ደቂቃ በስልክ ማነጋገር እፈልጋለሁ አልኩት። ሚስተር ኡተር ሳያቅማማ ወዲያውኑ ከዚያው ከብሌር ሐውስ ስልክ ደውሎ አገናኘኝ። የስቴት ዲፓርትመንት ባዘጋጀው ፕሮቶኮል የንጉሠ ነገሥቱ የቀኝ እጅ የሆኑት ትልቁ ባለሥልጣን የጽሕፈት ሚኒስትሩ በዋይት ሐውስ በሚደረገው ንግግር ከጃንሆይ ጋር ሆነው እንዲካፈሉ በፕሮግራሙ አልተገለጸም። በአገራችን የጽሕፈት ሚኒስትር ማለት ከሚኒስትሮች ሁሉ ከፍተኛ ሥልጣን ያለው ነው አልኩት። ሚስተር ደለስ ሐሳቤን ተቀብሎ ሚስተር ኡተር ፕሮግራሙን እንዲያስተካክል አዘዘው። በዚህ በጣም ደስ አለኝ። የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩን ፎስተር ደለስን የማውቀው ከብዙ ዓመታት በፊት በዩናይትድ ኔሽን የአሜሪካን አምባሳደር በነበረበት ጊዜ ነው። የኤርትራ ጉዳይ በተባበሩት መንግሥታት ጉባኤ በሚታይበት ጊዜ፤ ምንም እንኳ በአንዳንድ ሐሳብ ላይ ብንጋጭም፤ በጠቅላላው



ለኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት በዋሽንግተን ዋና ዋና መንገዶች ላይ
የአሜሪካ ሕዝብ መልካም አቀባበል ሲያደርግላቸው፤



ፕሬዚዳንት አይዘንሐወርና ባለቤታቸው በዋይት ሀውስ ዋና መግቢያ
በር ላይ ንጉሠ ነገሥቱን ሲቀበሏቸው፤

መልካም ግንኙነት ነበረን። አሁንም በጥሩ መንፈስ አነጋግሮ ሐሳቤን ስለተቀበለኝ በጣም ደስ አለኝ። ይህንን ከደለስ ጋር ያደረግኩትን ስምምነት ለጸሐፊ ትዕዛዝ ለመንገር ወደ ማረፊያቸው ስሄድ፣ አማካሪዬ ስፔንሰር እየሮጠ መጣና፣ " .... ነገ ጠዋት ጃንሆይ ከፕሬዚዳንቱ ጋር በዋይት ሐውስ በሚነጋገሩበት ጊዜ፣ የፔንታጐን ባለሥልጣኖች (የአሜሪካ የጦር ሚኒስቴር) ከጦር ሚኒስትሩ ከጄኔራል ዓቢይ ጋር፣ ኢትዮጵያ ስለሚያስፈልጋት የጦር መሣሪያ ጉዳይ ለመነጋገር ፕሮግራም አዘጋጅተዋል .... " አለኝ። ጸሐፊ ትዕዛዝ ከጃንሆይ ጋር ወደ ዋይት ሐውስ ሲሄዱ፣ ዓቢይ ደግሞ ወደ ፔንታጐን ይሄዳል። ስለዚህ፣ ፕሮብሌሙ ሁሉ መፍትሔ የተገኘለት መሆኑን በዝርዝር ለጸሐፊ ትዕዛዝ አስረዳኋቸው። ከአኳኋናቸው እንደተረዳሁት እኔ ስናገር የሚያዳምጡኝ በደስታ መንፈስ መስሎኝ ነበር። ነገር ግን የሰጡኝ መልስ የጠበቅኩት አልነበረም። « እንደምታውቀው አሜሪካኖቹ ይህን ፕሮግራም በድንገት ብቅ አላደረጉትም። እኔን ደብቃችሁኝ ነው እንጂ፣ አንተና ይልማ ገና ከአዲስ አበባ ሳንነሣ አውቃችሁታል። አሁን አንድ ሰዓት ባልሞላ ጊዜ ውስጥ፣ በቴሌፎን የጨረስከውን ጉዳይ ገና ከአዲስ አበባ ሳንነሣ ከዚሁ ከወዳጅህ ከደለስ ጋር በቴሌግራም ተላልከህ ማስተካከል ትችል ነበር። ጋባዦቻችን አሜሪካኖችም ቀደም ሲል አዘጋጅተው ያስራጩትን ፕሮግራም፣ ዛሬ የኔን ስም ለመጨመር ሲሉ የታተመውን እየደለዙ ከማሻሻል ይድኑ ነበር » አሉኝ።

ይህ የዘለፋ አነጋገራቸው በጣም ስለነካኝ መልስ እንድሰጣቸው አስደፈረኝ። « .... ይስሙኝ ጸሐፊ ትዕዛዝ ! እርስዎ ሰው የሚሠራውን በመብራት እየተከታተሉ መልቀምና ማሳዘን ሲያውቁበት፣ በሌላ በኩል ደግሞ እርስዎ በአሠራርዎ በሰው ላይ ምን ያህል ችግር እንደሚፈጥሩ አይታይዎትም። .... » አልኳቸው። ከወንበራቸው ብድግ ብለው፣ በረጋ መንፈስ ጥያቄ አቀረቡልኝ። « እኔ እንደማንም ሰው በምሠራው አልሳሳትም ብዬ አልከራከርም። ሆኖም ካደረግሁት ስሕተት አንተ የምታውቀውን አንድ ምሳሌ ብትሰጠኝ በጣም ደስ ይለኛል » አሉኝ። እኔም ጥያቄያቸው ደስ ስላለኝ፣ አንድ ጥሩ ምሳሌ ሰጠኋቸው። ይኸውም ይህንኑ የአሜሪካኑን ጉብኝት በሚመለከት ጉዳይ ነው። « .... በሳምንት ቢያንስ ሦስት ጊዜ ውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር እየመጡ፣ ቢሮዬን ይዘው፣ ሠራተኞቼን እየሰበሰቡ፣ የአሜሪካንን አምባሳደር፣ ካውንስለሩንና ሚሊታሪ አታሼውን እየጠሩ፣ የጉብኝቱን ዝርዝር ፕሮግራም ሲያዘጋጁ፣ እኔን ጉዳዩ በቀጥታ የሚመለከተኝን ሚኒስትር፣ ከዝግጅቱ ውጭ ማድረግዎ አልታየዎትም ወይ? .... በዚህም አሠራርዎ የአሜሪካን አምባሳደር ተገርሞ አክሊሉ ከውጭ ጉዳይ ሚኒስትርነቱ ተሽሯል ወይ? ብሎ እስከ መጠየቅ መድረሱን ሰምተው የለም ወይ ? ...እንግዲህ ! እርስዎ እንደ ውጭ ጉዳይ ሚኒስትር ሆነው፣ ቢሮዬን ይዘው፣ ሥልጣኔን ወስደው፣ ባዘጋጁት ፕሮግራም ለደረሱት አንዳንድ ስሕተቶች ተጠያቂነቴ ምን ላይ ነው ? ..... » አልኳቸው። መቼም የሚመልሱት አያጡም። ወዳጆቼና ወንድሞቼ በሚጠሩኝ በቤት ስሜ፣ " አክሊል " አንድ ጊዜ አዳምጠኝ አሉኝ። « .... እኔ አቢሮህ እየመጣሁ ይህንን የአሜሪካን ጉብኝት ያዘጋጀሁት፣ ለአንተ በመጨነቅና በማሰብ ጃንሆይ የሚጥሉብህን ችግር እኔ ልሸከምልህ ብዬ ነው እንጂ፣ በአንተ ሥራ ለመግባትና አንተን ለማሳዘን አልነበረም። ታስታውሳለህ ? ..... ጃንሆይ የመጀመሪያቸውን የኦፊሲየል ጉብኝት ማድረግ አጥብቀው የፈለጉት በእንግሊዝ አገር ነበር። በዚያን ጊዜ አንተ የንጉሠ ነገሥቱ ጉብኝት የሚጀመረው አሜሪካ ቢሆን ይሻላል፣ የሚል ሐሳብ ባቀረብክ ጊዜ፣ ከጃንሆይ ጀምሮ ንጉሣዊው ቤተሰብ በሙሉ፣ በተለይም ልዑል ራስ ካሣ ይኸ ልጅ ከመንገድ እየወጣ እንግሊዞችን ይቃወማል በማለት እንደዚያ ሲወርፉህ ማን ነበር አጠገብህ የቆመልህ ? ..... አቶ



የኒውዮርክ ከንቲባ ቫግነር፤ ለንጉሠ ነገሥቱ የክብር ነዋሪነት ሜዳይ ሲያጠልቅላቸው፤



የተባበሩት መንግሥታት ዋና ጸሐፊ ዳግ ሐመርሾልድ፤ ለንጉሠ ነገሥቱና
ለክብር ተከታዮቻቸው ባደረጉት የራት ግብዣ ላይ፤

አክሊሉ የአሜሪካ ጉብኝት ይቅደም ያለው፤ ጣልያን ከአገራችን ከተባረረ በኋላ እንግሊዞች ነፃነታችንን በመድፈር በጃንሆይና በመንግሥታቸው ላይ የተበተቡትን ተንኮል ለማፍረስ የደረሱልን አሜሪካኖች ናቸው በማለት ነው እንጂ፤ በተለይ እንግሊዞችን ለመቃወም አይደለም ብዬ የተሟገትኩልህ እኔ ብቻ መሆኔን ትረሳለህ? በመጨረሻው እንግሊዞች የጉብኝቱን ቀን በየጊዜው እየለዋወጡና እያራዘሙ ስለአስቸገሩ፤ የአሜሪካው ጉዞ እንዲቀድም ከተወሰነ በኋላ፤ ዝግጅቱ የተዋጣና እንከን የሌለበት እንዲሆን በማሰብ፤ የምወደው ወንድሜ፣ ትንሹ ወንድሜ፣ ያሳደግኩት ወንድሜ፣ እቢሮው ድረስ እየመጣሁ ፕሮግራሙን ያዘጋጀሁት አንተን ለመርዳት ነው እንጂ፤ ለእኔ ለወልደጊዮርጊስ ምን ጥቅም ያመጣል ብለህ ታስባለህ? .... የአሜሪካንም አምባሳደር አክሊሉ ውጭ ጉዳይን ለቅቋል ወይ? ብሎ እስከ መጠየቅ የደረሰው፤ የእኔን ወደ አንተ ቢሮ መመላለስ የተለየ ትርጉም እየሰጡ፤ ጓደኞችህ እነ መኮንን ደስታ የሚያናፍሱትን ወሬ ሰምቶ ነው እንጂ፤ በመሠረቱ የንጉሠ ነገሥቱ የአሜሪካ ጉብኝት በሚዘጋጅበት ጊዜ፤ የጽሕፈት ሚኒስትሩ ኃላፊ ሆኖ መታየት የለበትም በማለት አይደለም። ይልቅስ ካነሣኸው እኔ በአንተ ላይ ቅር ተሰኝቼ የሚከነክነኝን ጉዳይ ልገልጽልህ እፈልጋለሁ። ይኸውም፤ ጃንሆይ ዋሽንግተን ሲደርሱ የአሜሪካ ፕሬዚዳንት አውሮፕላን ጣቢያ ተገኝቶ አለመቀበሉ ነው።

ይህ ጉዳይ በጣም አሳዝኖኛል። አንተና ይልማ ግን ምንም አልተሰማችሁም። እርግጥ ! የዋይት ሐውስ ቤተመንግሥት ፕሮቶኮል፤ ፕሬዚዳንቱ የውጭ አገር መሪዎችን አውሮፕላን ጣቢያ ድረስ ሄዶ አይቀበልም የሚል ደንብ ማውጣቱን ሰምተናል። ሆኖም፤ ይህ ደንብ ለመሪዎች ሁሉ እኩል የሚሠራበት ነው ብዬ አላምንም። አንተ ግን የተባለውን ሰምተህ ዝም ከማለት አንድ ሙከራ ማድረግ ነበረብህ እላለሁ። ይኸውም፤ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ የአንዲት የታሪክ ጌታ፤ የሀብትና የሥልጣኔ ደሃ የሆነች የሩቅ አገር መሪ ቢሆኑም፤ ለነፃነት ባደረጉት ተጋድሎ፤ የፋሽስት ግፍ የተፈጸመባቸው፣ የዓለም መንግሥታት ማህበር ፍርድ የነፈጋቸው፣ በመጨረም መከራንና ፈተናን በቆራጥነት ተቀብለው ያሳለፉና ድልን ለማግኘት የበቁ ታላቅ መሪ በመሆናቸው፤ ዤኔራል አይዘንሐወር አውሮፕላን ጣቢያ ተገኝቶ ሊቀበላቸው የተገባ ነበር። የዓለም ሰላም ጠንቅ ሆነው የተነሡትን ናዚስቶችንና ፋሽስቶችን ተዋግቶ ድል ያደረገ የጦር መሪ ነው፤ ተብሎ የተነገረለት አይዘንሐወርም፤ ተመሳሳይ ተጋድሎ ለፈጸሙት ለቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ተገቢውን ክብር ቢሰጣቸው የራሱንም ታሪክ ሊያዳብርለት ይችል ነበር። ይህንንም ለማስረዳትና ለማስፈጸም ከአንተ የተሻለ ጠበቃ፣ ካንተ የተሻለ ዲፕሎማትና ዘዴ ዐዋቂ አልነበረም። ነገር ግን ለዚህ ጉዳይ አንዳች የተለየ ሙከራ ሳታደርግ የቀረኸው፤ ምናልባት አሁን እንደነገርከኝ፤ ወልደጊዮርጊስ በሥራዬ ገብቶ፣ ቢሮዬንና ሠራተኞቼን ወርሶ የዝግጅቱን ኃላፊነት ከወሰደ፤ እሱ እንደ ጀመረው እሱ ይወጣው ብለህ ይሆናል። ምክንያቱ ይህ ከሆነም፤ እውነት የለህም አልልም። እንዲያውም ወቀሳዬን ካንተ ላይ አንሥቼ ወደ እኔ አዛውረዋለሁ። .... እንደምታውቀው የዚህ የአሜሪካው ጉዞ ዝግጅት ሲጀመር አንዳንድ እንቅፋት እየተደነቀረ በመካከላችን አለመግባባት ፈጥሮብን ነበር። በዚህ ጊዜ ሁለታችንም በየአዕምሮአችን የተቀረፀውን ስሜት ቀድሞ እንደምናደርገው ተገላልጠን ባለመነጋገራችን ስሕተት አድርገናል። መቼም ሰው ስሕተቱን ከተረዳ ጥፋተኛ ነው አይባልም። አሁንም ሁለታችንም ያለፈውን ሁሉ እንተወውና የወደፊቱን ብቻ እናስብ። እኔ አንተን ከመውደዴና የዲፕሎማሲ ችሎታህን ከማድነቄ በስተቀር አንዳች ቂም የለኝም። .... ብለው ከወንበራቸው ተነሥተው ሳሙኝ። እኔም ሰላም በመውረዴ ደስ አለኝ።

ወደ ማረፊያዬ ተመልሼ እኝህ ሰው የተናገሩትን ሁሉ ስመረምር፣ በጣም ተገረምኩ። የሐሳብ አገላለጽ ችሎታ ስላላቸውና አቀራረቡንም ስለሚያውቁበት ነው እንጂ፣ የተናገሩት ሁሉ ትክክል አልነበረም።

1. ውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር እየመጡ ቢሮዬን ይዘው ያን ሁሉ ነገር ሲያተራምሱት የነበረው፣ አሁን ጊዜው ካለፈ በኋላ፣ እኔን አክሊሉን ጃንሆይ ከሚያደርሱብኝ ችግር ለማዳን አስቤ ነው የሚል ምክንያት ሰጡ። እንግዲህ እሳቸው እንዳሉት ዓላማቸው እኔን ለመርዳት ከሆነ፣ የአሜሪካንን አምባሳደርና ዲፕሎማቶቹን እየሰበሰቡ ሲያነጋግሩና ፕሮግራሙን በዝርዝር ሲያዘጋጁ ፤ እኔን ከጉዳዩ ውጭ ማድረግ አልነበረባቸውም።

2. አይዘንሐወር አውሮፕላን ጣቢያ ተገኝቶ ጃንሆይን ባለመቀበሉ የገለጹት አስተያየት፣ በሌላ አነጋገር አክሊሉ አንዳች ሙከራ አላደረገም ለማለት መሆኑ ግልጽ ነው። ጃንሆይ በዚህ አኳኋን ጉዳዩን ቢሰሙ፣ እውነት ነው ብለው በእኔ ላይ አንድ ዓይነት አስተያየት እንደሚወስዱ አይጠረጠርም። ስለዚህ፣ ጸሐፊ ትዕዛዝ በዚህ ጉዳይ ላይ የጃንሆይን ትልቅነት እየካቡ አይዘንሐወር ሲቀበላቸው ይገባ ነበር፣ በማለት የተናገሩት ሁሉ፣ ከልባቸው የሚያምኑበትን ሳይሆን፣ የእኔን ደካማነት የሚያሳይ አንድ ማስፈራሪያ ያዘጋጁ መሆናቸውን እንዳውቀው ለማድረግ ነው።

3. የጃንሆይ የውጭ አገር ጉብኝት የሚጀመረው በእንግሊዝ አገር ከሚሆን፣ በአሜሪካ ቢደረግ ይሻላል የሚለውን ሐሳብ ያቀረብኩት፣ ከሁሉ በፊት ከጸሐፊ ትዕዛዝ ጋር በረዥሙ ተነጋግሬ፣ እሳቸውም ሐሳቡን አጥብቀው የሚደግፉት መሆኑን ካረጋገጡልኝ በኋላ ነበር። ጉዳዩ ሲቀርብ፣ ጃንሆይና ራስ ካሣ፣ ንጉሣዊው ቤተሰብ ጭምር፣ አክሊሉ ከወዳጆቻችን ከእንግሊዞች ጋር ሊያጣላን ነው ብለው ሲቆጡ፣ ጸሐፊ ትዕዛዝ ተጋፍጠው መከራከራቸው እውነት ነው። ይሁን እንጂ ዛሬ ይህን ያለፈ ታሪክ አስታውሰው ሲናገሩ፣ « ..... ካንተ ጉን ቆሜ ተሟግቼ ያሸነፍኩልህን እንዴት ረሳኸው? ..... » የሚል ወቀሳ የሰነዘሩብኝ፣ የቀረበው ሐሳብ የእኔ ብቻ ሳይሆን፣ እሳቸው ያመኑበትና የደገፉት መሆኑን ሊጠቅሱት አለመፈለጋቸው እጅግ አስገረመኝ።

እንግዲህ ! የጃንሆይ መንግሥት ባለሙሉ ሥልጣን የሆኑት ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ፣ ማናቸውንም ጉዳይ እሳቸው እንደሚመቻቸው መልኩን እየለዋወጡ ለማቅረብና ለማስረዳት፣ ከዚያም በላይ ለማሳመን የተለየ ጥበብ ስለአላቸው፣ ከእሳቸው ጋር ክርክር መቀጠል ሌላ ጣጣ ማስከተል ስለሚሆን፣ የተናገሩትን የዕርቅ መንፈስ እሺ ብዬ ተቀበልኩ።

የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር አክሊሉ ሀብተወልድ ከዚህ በላይ እንደገለጹት፣ የዋሽንግተኑ ፕሮግራም እንደምንም በደህና ቢፈጸምም፣ ለአሜሪካ ፕሮቶኮል ያልታደሉት ጸሐፊ ትዕዛዝ፣ በኒውዮርክ ያልታሰበ ሌላ ችግር ጠበቃቸው። የኒውዮርክ ከንቲባ ቫግነር፣ (Mayor Vagner) ለቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ክብር ባዘጋጀው ትልቅ የምሳ ግብዣ ላይ ለጄኔራል ዓቢይና ለጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ በስማቸው ወንበር ሳይያዝላቸው በመቅረቱ፣ ሁለቱ ታላላቅ ሰዎች አዳራሹን ለቅቀው ወደ ሆቴላቸው ተመለሱ። በዚህ ጊዜ በአዳራሹ ውስጥ የታየው

የአስተናጋጆቹ መደናገጥና የተጋባዦቹም መገረም የደረሰውን ኃፍረት ሊሸፍነው አልቻለም። ይህን ከባድ ስሕተት የፈጸመው ማነው? አስተናጋጆቹ በመጀመሪያ የንጉሡን የክብር ተከታዮች ሊስት የኢትዮጵያ ኤምባሲ አሟልቶ ስላልሰጠን ነው የሚል ምክንያት ለመስጠት ፈለጉ። የትኛው ኤምባሲ? የዋሽንግተኑ? ወይስ የኒውዮርኩ? ..... በዚያን ጊዜ በኒውዮርክ (U.N) አምባሳደር የነበሩት አቶ ዘውዴ ገብረሕይወት (ኋላ ቢትወደድ) የእኔ ኃላፊነት ጃንሆይ የተባበሩት መንግሥታት ድርጅትን ሲጎበኙ ነው እንጂ፣ የአሜሪካ አድሚኒስትሬሽን በሚያዘጋጀው ፕሮግራም ውስጥ የለሁበትም አሉ። የፈረደባቸው አቶ ይልማ አሁንም ጥርስ ውስጥ ገቡ። በዚህ በደረሰው ሁኔታ ጃንሆይም በጣም ስለአዘኑ፣ አምባሳደር ይልማ ሰላም አላገኙም። የጄኔራል ዓቢይና የጸሐፊ ትእዛዝ ወልደጊዮርጊስ ስም በምን ምክንያት እንደተሰረዘ ምርምሩ እየጋለ ሲመጣ፣ ከከንቲባ ቫግነር ቢሮ ውስጥ አንድ ሚስ ማርጋሬት የተባለች ጸሐፊ ከመጋረጃ ውስጥ ብቅ አለች።

ከግብዣው ሦስት ቀን በፊት ለምሳው ዝግጅት ኃላፊ የሆነው የፕሮቶኮል ሹም፣ ከንጉሠ ነገሥቱ ተከታዮች መካከል መጥራት የምንችለው ሰባት ሰዎች ብቻ ስለሆነ፣ እነዚህ ሰባቱ ባለሥልጣኖች ማን ማን ሊሆኑ እንደሚገባ፣ ከኢትዮጵያ አምባሳደር ጋር ተነጋግረሽ አስወስኝልኝ ብሎ ጠየቀኝ። ወዲያው ዋሽንግተን ስልክ ስደውል፣ አምባሳደሩ ባለመኖሩ ከረዳቶቹ ዲፕሎማቶች አንዱ ቀርቦ አነጋገረኝ። የምፈልገውን ስገልጽለት፣ ጉዳዩ ቀላል ነው እኔ እነግርሻለሁ ብሎ፣ የሚከተሉትን የሰባቱን ሰዎች ስም ዝርዝር ሰጠኝ።

1. ልዑል ሣህለሥላሴ /የጃንሆይ ልጅ/፣
2. ልዕልት ሰብለ ደስታ /የጃንሆይ የልጅ ልጅ/፣
3. አክሊሉ ሀብተወልድ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር፣
4. ይልማ ዴሬሣ የንጉሠ ነገሥቱ አምባሳደር፣
5. ተፈራወርቅ ኪዳነወልድ ሼፍ.ደ.ካቢኔ /ልዩ ጸሐፊ/፣
6. ዘውዴ ገብረሕይወት በኒውዮርክ (U.N) አምባሳደር፣
7. ኮ/መኰንን ደነቀ ዋና የልፍኝ አስከልካይ ናቸው።

ይህን ዝርዝር በጥሩ እንግሊዝኛ የነገረኝን ዲፕሎማት ስምና ደረጃውን ጠይቄ በማስታወሻዬ ላይ ባለማስፈሬ ጥፋተኛ ነኝ። ነገር ግን የተጠሩትን የሰባቱን ተጋባዦች ስም ያገኘሁት ከኢትዮጵያ ኤምባሲ እንጂ፣ እኔ አልፈጠርኩትም ብላ፣ ሚስ ማርጋሬት ራፖሯን ዘረገፈች። እንግዲህ፣ ሁኔታው ሲታይ ስሕተቱ የተፈጸመው በከንቲባ ቫግነር ቢሮ ሳይሆን ዋሽንግተን ዲሲ በሚገኘው የኢትዮጵያ ኤምባሲ ዘንድ መሆኑ የሚያከራክር አልሆነም። የሰባት ዋና ዋና ተከታዮች ስም እንዲሰጥ ሲጠየቅ፣ ታላላቆቹን ጄኔራል ዓቢይንና ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስን ትቶ፣ የአቶ ተፈራወርቅንና የአቶ ዘውዴ ገብረሕይወትን ስም የሰጠው ዲፕሎማት፣ በተንኮል እንጂ በቀና መንፈስ አለመሆኑ ለማንም ግልጽ ነው። በኤምባሲው ውስጥ ያሉት ዲፕሎማቶች ከአማካሪው ጀምሮ እስከ ፕሬስ አታሼው ተጠይቀው፣ ሁሉም እኛ አይደለንም ስላሉ፣ ድምፃቸው በቴፕ ተቀድቶ ለከንቲባ ቫግነር ጸሐፊ ቢቀርብላት፣ ያነጋገራትን ሰው በድምፁ መለየት ትችላለች ብለው የአሜሪካ የፀጥታ ሰዎች ለአምባሳደሩ ሐሳብ አቅርበው ነበር። አቶ ይልማ ግን በአገሬ ኤምባሲ የውስጥ ጉዳይ እናንተን አይመለከትም ብለው መለሷቸው። በመጨረሻውም ይህን የፕሮቶኮል ችግር ፈጥሮ ቅያሜና ቅሬታ ያስከተለው

ተንኮለኛው ዲፕሎማት ማን መሆኑ በይፋ ሳይገለጽ፣ በአሜሪካ የሚደረገው የኦፊሲየል ጉብኝት ተፈጽሞ ንጉሠ ነገሥቱ ወደ አገራቸው ተመለሱ።

ይህን የመሰለው የፕሮቶኮል ችግር እንደ አገር ጉዳይ ታሪክ ሆኖ ሲቀርብ፣ የዛሬው ትውልድ በቀድሞዎቹ የኢትዮጵያ ባለሥልጣኖች ላይ አንድ ዓይነት የንቀፌታ አስተያየት ለመስጠት ይቃጣ ይሆናል። ነገር ግን፣ ፕሮቶኮል የእያንዳንዱን ሰው መብት በትክክል ሲጠብቅ ምን ያህል እንደሚያረካ፣ በስሕተት ምክንያት ደግሞ የአንዱን ደረጃ ከሌላው አሳንሶት ሲገኝ፣ ምን ያህል ቅር እንደሚያሰኝ ለመረዳት የሚቻለው፣ ስለ ፕሮቶኮል የሚያውቅና ራሱም ተካፋይ ሆኖ የቀመሰው ብቻ ነው። ፕሮቶኮል፣ በሥልጣኔ በገፉትም ሆነ ወይም ኋላ ቀር በተባሉት አገሮች ምንጊዜም የሚሠራበት፣ አስፈላጊነቱም የማያጠራጥር የሥርዓት ማስከበሪያና ማስፈጸሚያ ደንብ ነው። በተለይ የፕሮቶኮል ድንጋጌ በከፍተኛ ጥንቃቄ የሚሠራበትና ብርቱ ቁጥጥር የሚበዛበት፣ «ሬቮሉሽናሪ» እየተባሉ ይጠሩ በነበሩት በሶቪየት ሕብረትና በሕዝባዊ ቻይና መንግሥታት ዘንድ እንደነበረ ብዙዎቻችን በዕድሜያችን ደርሰን አይተነዋል።

ስለዚህ፣ በዚህ ምዕራፍ ላይ እንደተተነተነው፣ በቀዳማዊ ኃይለሥላሴ የአሜሪካ ጉብኝት ጊዜ፣ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ የደረሰባቸውን የፕሮቶኮል ጥቃት፣ በጥልቀት የተመለከተ፣ ቅያሜያቸውን ሆነ ቅሬታቸውን ለመረዳት አያዳግተውም። ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ በዚያን ዘመን ለዐሥራ አራት ዓመታት ያንን ሁሉ ሥልጣንና ያንን ሁሉ ክብር ከተጐናጸፉ በኋላ፣ እሳቸው በረዷቸውና ሲታዘዟቸው በነበሩት ሰዎች የፕሮቶኮል ወንበራቸው ሲወሰድባቸው፣ ሐዘናቸው ሆነ ብስጭታቸው ተገቢ አልነበረም የሚል ሊኖር አይችልም። ቀዳማዊ ኃይለሥላሴም፣ ወጣቱ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትራቸው ከትልቁ ባለሥልጣን ከጸሐፊ ትዕዛዛቸው በፕሮቶኮል እንዲቀድም መታሰቡን ሲሰሙ፣ "አሜሪካኖች ያዘጋጁትን መቀበልና መፈጸም ነው" ሲሉ ለአምባሳደራቸው ለይልማ ዴሬሣ የሰጡት ፈጣን መምሪያ፣ በዚያን ዘመን ከወልደጊዮርጊስ ለመለያየት ያዘነበሉበት ጊዜ ስለሆነ ነው እንጂ፣ ቀደም ሲል በነበረው የፍቅሩ ዘመን ቢሆን ኖሮ፣ አባጠቅል ራሳቸው ከአሜሪካን አምባሳደር ጋር ተነጋግረው ፕሮቶኮሉን ያስለውጡት ነበር። ምን ይሆናል ? ጊዜው በወልደጊዮርጊስ የሥልጣን ሕይወት ላይ በመጠኑም ቢሆን ጳመና የጣለበት ስለሆነ፣ ገና ከጠዋቱ እጅግ በደከሙበት በዚህ በአሜሪካ ጉብኝት ላይ፣ በደረሰባቸው ሁሉ ብስጭታቸውን በልባቸው አምቀው ወደ አገራቸው ተመለሱ።

# ምዕራፍ ፬

## ጃንሆይ በአሜሪካ ጉዞ ላይ ሆነው የአልጋወራሽ ተጠባባቂነት

ልዑል መርዕድ አዝማች አስፋወሰን፣ አልጋወራሽ ከሆኑበት ከሐያ ሦስት (23) ዓመታት በኋላ ለመጀመሪያ ጊዜ፣ ንጉሠ ነገሥቱ ለዐሥር ሳምንታት ከአገር ውጭ የባሕር ማዶ ጉዞ በሚያደርጉበት ሰዓት፣ በአምሳለ ገነት ጽሕፈት ቤት በአባታቸው ወንበር ሆነው፣ የኢትዮጵያን አስተዳደር በተጠባባቂነት እንዲመሩ ኃላፊነት ተሰጣቸው።

የተሰጣቸውም ሥልጣን፣ ጃንሆይ እንደሚያደርጉት የካቢኔ ሚኒስትሮችን በዓቃቤ ሰዓት እየተቀበሉ በማነጋገር፣ ለሚያቀርቡላቸው ጉዳዮች ጠቅላይ ሚኒስትሩ ቢትወደድ መኮንን እንዳልካቸውና የአገር ግዛት ሚኒስትሩ ራስ አበበ አረጋይ ግራና ቀኝ ወንበር ተሰጥቷቸው በምክር እየረዷቸው፣ አስፈላጊውን ውሳኔ መስጠት ሲሆን፣ ከዚህ ቀጥሎ ደግሞ ከሰኞ እስከ ዓርብ ዘወትር በቀን አንድ ሰዓት በሚከናወነው የዙፋን ችሎት ላይ እየተገኙ፣ የአባታቸውን ቦታ ይዘው "ከሙት በቃ" በስተቀር ሌሎቹን የይግባኝ ክሶች በሚመስላቸው እንዲፈርዱ ተደርጕ ነበር።

አልጋወራሽ አስፋወሰን ይህንን የሥልጣን ዕድል ያገኙት ለመጀመሪያ ጊዜ ስለሆነ፣ በጣም ተደስተው የሚቀርቡላቸውን ሥራዎች እያፋጠኑ በመወሰንና ከካቢኔ ሚኒስትሮቹም ጋር የመግባባት መንፈስ በመፍጠር፣ ከግርማዊ አባታቸው የተለየ የአመራር ሁኔታ አሳዩ። ይኸውም፣ ሚኒስትሩ እስካሁን ሠርቶ ያገኘውን ውጤትና ወደፊትም ለመሥራት የዘረጋውን ፕላን ዘርዝሮ ሲያስረዳ፣ ተጠባባቂው ንጉሠ ነገሥት በፈገግታ በማዳመጥና ሚኒስትሩ የጠየቀውንም ተጨማሪ ወጭ ወዲያውኑ በመፍቀድ የሚሰጡት አስደሳች ውሳኔ ነበር። አንዳንዶቹ ሚኒስትሮች፣ ይህ አሠራር ከሚጠብቁት በላይ ስለፈጠነባቸው፣ ዘለቄታ አይኖረውም ብለው ብዙ ጉዳዮችን ከማቅረብ ሲቆጠቡ፣ ሌሎቹ ደግሞ በዚህ አጋጣሚ የተገኘውን ዕድል ለመጠቀም ስለፈለጉ፣ የየሚኒስቴራቸውን የሥራ ፕሮግራም በማስፋፋት፣ ለዓመቱ ከተመደበላቸው በጀት እያለፉ ተጨማሪ ወጭ እንዲሰጣቸው ማመልከቻዎቻቸውን ለማቅረብ ተሽቀዳደሙ። ልዑል አልጋወራሽም፣ ሚኒስትሩ ያዘጋጀውን የሥራ ፕሮግራም በማድነቅ፣ " .... ለአገር ጥቅም የሚሰጥ ማለፊያ የሥራ ዕቅድ ስለሆነ፣ የጠየቀው ገንዘብ ከድንገተኛ ወጭ በአስቸኳይ እንዲሰጠው ፈቅጃለሁ .... " የሚለውን ትዕዛዝ በጽሕፈት ሚኒስቴር ማዘዣ ለገንዘብ ሚኒስትሩ ለአቶ መኮንን ሀብተወልድ እያከታተሉ መላካቸውን ቀጠሉ።

ንጉሠ ነገሥቱ ጉዞአቸውን በጀመሩ በአንድ ወር ጊዜ ውስጥ፣ የጃንሆይ ተጠባባቂ በሆኑት በልዑል አልጋወራሽ ፈቃድ፣ ከድንገተኛ ወጭ በጀት ላይ ለየሚኒስቴሩ እንዲከፈል የታዘዘው ወጭ፣ ከአንድ ሚሊዮን ብር ማለፉን አቶ ምናሴ ለማ የገንዘብ ም/ሚኒስትር ሲያዩ፣ ከፍ ባለ ድንጋጤ አቶ መኮንን ሀብተወልድ ቢሮ ገብተው ምን ይሻላል? ሲሉ ጠየቁ። አቶ መኮንን ሁለት ዓይነት ሐሳብ ሰጧቸው።

1ኛ/ በአልጋወራሽ ትዕዛዝ ከጽሕፈት ሚኒስቴር የሚጐርፉትን ማዘዣዎች "ታይቷል ይቀመጥ" እያልክ መዝገብ ቤቱ የተለየ ፋይል ከፍቶ እንዲያኖራቸው በማድረግ ዝም በል።

2ኛ/ ይህን ማድረግ ቅር የሚልህ ከሆነ፣ በቀጥታ አምባሰል ገነት ሄደህ ለአልጋወራሽ ችግራችንን ዘርዝረህ አስረዳ፣ አሏቸው።

አቶ ምናሴ ሁለተኛውን ሐሳብ መርጠው አምባሰል ገነት ሄደው አልጋወራሽን አገኟቸው። " .... ጌታዬ የመጣሁት ችግር ስለአጋጠመን ስለሆነ፣ ለመናገር ይፍቀዱልኝ .... " ብለው ጠየቁ። አልጋወራሽ እንዲናገሩ ፈቀዱላቸው።

" ...... በዚህ በአንድ ወር ጊዜ ውስጥ ከድንገተኛ ወጭ፣ ለአንዳንድ ሚኒስትሮች እንዲከፈል ልዑል ጌታዬ ያዘዙት አንድ ሚሊዮን አንድ መቶ ሀምሳ ሺህ ብር ደርሷል። እኛ ዛሬ ያለን የዓመቱ በጀት አንድ ሚሊዮን አምስት መቶ ሺህ ብር ብቻ ነው። ከዚህ ውስጥ በልዑል ጌታዬ የተፈቀደውን በሙሉ ብንከፍል፣ ባዶ እጃችንን እንደቀረን ይቆጠራል። ነገ በአገራችን ላይ ምን አደጋ እንደሚደርስ ማናችንም አናውቅም። ስለዚህ፣ ገንዘቡ የታዘዘላቸውን ሚኒስትሮች ሁሉ ልዑል ጌታዬ ጠርተው እንዲታገሡ ቢነግሯቸው ከጭንቀታችን እንድናለን .... " አሉ። የአቶ ምናሴን ሐሳብ አልጋወራሽ ካዳመጡ በኋላ፣ የሚከተለውን መለሱላቸው።

" .... መጀመሪያ አለቃህ የገንዘብ ሚኒስትሩ አንተን ይዞ እኔ ዘንድ መምጣት ያልቻለው በምን የተነሣ ነው? ሁለተኛ ገንዘቡ የታዘዘው ለአስቸኳይና በጣም አስፈላጊ ለሆኑ ሥራዎች ስለሆነ፣ አንተና አለቃህ የምታቀርቡትን ምክንያት አልቀበለውም። " .... እኔ በሚመስለኝ ፈቅጄ ትዕዛዜ ከተላለፈ በኋላ፣ ሚኒስትሮቹን እየጠራሁ ሐሳባችሁን ለውጡ አልልም። አንተና አለቃህ የታዘዛችሁትን መፈጸም አለባችሁ .... " ብለው አሰናበቷቸው። አቶ ምናሴ ለማ በጣም ደነገጡ። አልጋወራሽ ኃይለኛ ሆነዋል። ድሮ የማውቃቸው አልሆኑም። በጣም ተለውጠዋል። ካሉ በኋላ፣ ወደ አቶ መኰንን ሀብተወልድ ቢሮ ሄደው፣ "ጌቶች አልጋወራሽ በጣም ተቆጥተዋል" በሚል መነሻ ከላይ የተገለጸውን ሪፖርት አቀረቡ። በዚህ ጊዜ አቶ መኰንን ሀብተወልድ ሐሳቤንና የማምንበትን ለአልጋወራሽ በጽሑፍ ባቀርብላቸው ይሻላል ብለው፣ ልዩ ጸሐፊያቸውን አቶ አሰፋ ድፋዩን ጠርተው መስታወሻቸውን አዘጋጁ። ቃሉ የሚከተለው ነበር።

ልዑል ጌታዬ!

" ... አንዳንድ የንጉሠ ነገሥቱ ሚኒስትሮች ለየመሥሪያ ቤታቸው ጉዳይ ከድንገተኛ ወጭ በጀት ላይ ገንዘብ እንዲሰጣቸው ባመለከቱት መሠረት፣ ልዑል ጌታዬ በቸርነትዎ ለእኔ ለገንዘብ ሚኒስትሩ ያስተላለፏቸውን ማዘዣዎች በሙሉ በታላቅ አክብሮት አንብቤያቸዋለሁ። ለዚህ ጉዳይ የበኩሌን አስተያየት የማቀርብልዎ፣ ልክ ከዚህ ቀደም ለግርማዊ አባትዎ በምገልጸው ዓይነት መሆኑን እንዲያውቁልኝ አስቀድሜ እለምናለሁ።

የድንገተኛ ወጭ በጀት ስሙ እንደሚያመለክተው፣ በግርማዊ ንጉሠ ነገሥት መልካም ፈቃድና ትዕዛዝ በተግባር የሚውለው፣ በተለይ በአገርና በሕዝብ ላይ ያልተጠበቀ ድንገተኛ አደጋ ሲደርስ ነው። ይኸውም፣ እንደ መሬት መንቀጥቀጥ፣ እንደ ውሃ መጥለቅለቅ፣ እንደ አውሉ ነፋስ፣ እንደ ድርቀትና እህል

እጥረት የመሳሰለው አደጋ ሲደርስ፤ በአስቸኳይ የሚያስፈልገውን ወጭ በማድረግ፤ ችግሩን ለመቋቋም ነው። ነገር ግን፤ አሁን ጃንሆይ የሌሉበትን ጊዜ ጠብቀው፤ ሚኒስትሮቹ ከዚህ ከድንገተኛ ወጭ ልዑልነትዎ እንዲያዙላቸው ያቀረቧቸው ሐሳቦች፤ ከዚህ ቀደም ያልታቀዱና አስቸኳይነታቸውም ለምን እንደሆነ ያልተገለጹ ናቸው።

ለምሳሌ፤ የንግድና የኢንዱስትሪ ሚኒስትሩ፦ ነጋዴዎቹንና ባለ ኢንዱስትሪዎቹን እየሰበሰብኩ ለአገር ልማት ጉዳይ የምወያይበት አንድ አዳራሽ መሥሪያ ይፈቀድልኝ ብሏል። ይህንን ሐሳብ ባለፈው የበጀት ዝግጅት ላይ ለምን አላቀረበውም? .... አምና ካልተቻለው ደግሞ ለሚቀጥለው ዓመት በጀት ለምን አይሞክርም? ይህን አዳራሽ ዛሬ ለመሥራት አስቸኳይ የሆነው በምን ምክንያት ነው? .... ስለዚህ የቀረበው የበጀት ጥያቄ ድንገተኛ ወጭን አይመለከትም።

የእርሻ ሚኒስትሩ፦ ለከብት እርባታ ማስፋፊያ አስፈላጊ የሆኑትን ማዳቀያ ከብቶች ከውጭ አገር ለመግዛት ስምምነት አድርጌ ከፍያውን ለመፈጸም አልቻልኩም ብሎ አመልክቷል። እንግዲህ መጀመሪያ የእርሻ ሚኒስትሩ ይህንን ውል ሲያደርግ ከምን በጀት ለመክፈል አስቦ ኖርዋል? ... ለዚህ መልሱን አልሰጠም። ሆኖም ጉዳዩ የድንገተኛን በጀት የሚመለከት አይደለም።

የትምህርት ሚኒስትሩ፤፦ ለአዳሪ ትምህርት ቤቶች ማስፋፊያ ለዘንድሮ የተመደበልኝ በጀት ወጭውን ሊሸፍንልኝ ስላልቻለ፤ ከድንገተኛ በጀት ይታዘዝልኝ ሲል አመልክቷል። ሚኒስትሩ ፕላኑን አዘጋጅቶ ወጭው ከተተመነና ከተፈቀደ በኋላ፤ ምን ቢደርስበት ገንዘብ እንዳጠረው አላስረዳም። ይህም ሁኔታ እንዲቃናለት መጠየቅ ያለበት ለመጭው ዓመት በጀት እንጂ፤ ከድንገተኛ ወጭ መሆን የለበትም።

የጤና ጥበቃ ሚኒስትሩ፦ በዳግማዊ ምኒልክ ሆስፒታል የአንደኛና የሁለተኛ ደረጃ መኝታ ክፍሎችን ለማደስና ቁጥራቸውን ለመጨመር፤ የተጀመሩትንም ሥራዎች ለማስጨረስ ገንዘብ ስለአጠረኝ፤ ከድንገተኛ ወጭ ይታዘዝልኝ ሲል አመልክቷል። የ1946 ዓ.ም የበጀት ዓመት ሊጠናቀቅ የቀረው ሦስት ወራት ብቻ ነው። ስለዚህ፤ ጊዜውን ጠብቆ ለመጭው ዓመት በጀት መጠየቅ ይችላል። ደግሞም የተጠየቀው ወጭ ለሕዝብ ሕክምና አገልግሎት መስጫውን ሳይሆን፤ በምቾት ለሚታከሙት ሕሙማን ስለሆነ፤ አስቸኳይነቱ አይታየኝም።

ልዑል ሆይ፤

የድንገተኛ ወጭ በጀት ዓላማውና ግቡ ምን እንደሆነ በተቻለኝ ያስረዳሁ ይመስለኛል። በግርማዊ ጃንሆይ አሠራር አንድ ሚኒስትር የበጀት ችግር ሲገጥመው፤ ያቀረበው ከመፈቀዱ ወይም ከመከልከሉ በፊት፤ በጉዳዩ አግባብ ያላቸው ሰዎች አስተያየት እንዲሰጡበት ይደረጋል። ከእነዚህም ሰዎች መካከል አንዱ፤ እኔ የገንዘብ ሚኒስትሩ ነኝ። ልዑልነትዎ ወደፊት ይህን የመሳሰለው ጉዳይ ሲቀርብልዎ፤ የግርማዊ አባትዎን አመራር ቢከተሉ የተገባ ይመስለኛል። የገንዘብ ምክትል ሚኒስትሩ አቶ ምናሴ ለማ ለልዑልነትዎ እንዳስረዳው፤ እኔም በዚህ ማስታወሻዬ እንደገለጽኩት፤ እስካሁን የታዘዙትን ከአንድ ሚሊዮን ብር በላይ



አቶ ምናሴ ለማ
የገንዘብ ም/ሚኒስትር

የሆኑትን ወጭዎች፣ የገንዘብ ሚኒስቴር ለመክፈል የማይችል መሆኑን በታላቅ ትሕትና አመለክታለሁ።

ትሁት አገልጋይዎ
መኰንን ሀብተወልድ

አልጋወራሽ መርዕድ አዝማች አስፋወሰን፣ በዚህ መኰንን ሀብተወልድ በጻፉላቸው ማስታወሻ ተናደዱ። ከሁሉም ይበልጥ በጣም ያበሳጫቸው፣ የንጉሠ ነገሥቱ ተጠባባቂ በመሆናቸው፣ ለየሚኒስቴሩ እንዲከፈል ያዘዙትን ወጭ በሙሉ አልከፍልም ማለታቸው ነው። ይህ ትልቅ ድፍረት ነው። ባይሆን እስካሁን የታዘዘውን ከፍሎ ለወደፊቱ ሌላ ትዕዛዝ ለመቀበል መቸገሩን ማመልከት ነበረበት። በተጨማሪም እንደአስተማሪ ሆኖ ይህን ሁሉ ከመጻፍ፣ እቢሮዬ መጥቶ ራሱ ለምን አላስረዳም? ሌሎቹ ጓደኞቹ ሚኒስትሮች የተመደበላቸውን ዓቃቤ ሰዓት እያከበሩ እኔ ዘንድ ሲቀርቡ፣ እስካሁን ድረስ መኰንን ሀብተወልድ ብቅ ብሎ አያውቅም። ይኸ ሁሉ ሲታይ የማን አለብኝ ስሜት መሆኑ ግልጽ ነው። ... ካሉ በኋላ፣ " ... በዛሬው ዕለት አቶ መኰንን ሀብተወልድን ከወር ደሞዙ ሲሦውን (500) ብር መቅጣቴንና ለወደፊቱም ጠባዩን እንዲያሻሽል ከማስጠንቀቂያ ጋር ጻፍለት! ብለው አቶ ገብረወልድ እንግዳ ወርቅን አዘዙ። በዚያን ጊዜ የጽሕፈት ሚኒስቴር ዋና ዲሬክተርና ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ በሌሉበት ታላቁን የንጉሠ ነገሥቱን ማሕተም ያዥ የሆኑት አቶ ገብረወልድ፣ በጣም ተጨነቁ። "ይህ ጉዳይ ራስ አበበና ቢትወደድ መኰንን ባሉበት ቢመከርበት አይሻልም ወይ? ሲሉ ሐሳብ አቀረቡ። ተጠባባቂው ንጉሠ ነገሥት የሰጠሁት ውሳኔ አይሻሻልም። አንተም የታዘዝከውን አሁኑኑ ደቂቃ ሳታሳልፍ ፈጽም! ብለው ተቆጡ። አቶ ገብረወልድ መከራከሩ ውጤት የማይሰጥ ስለሆነ፣ በታዘዙት መሠረት ማዘዣውን ጽፈው በአደራ ላኩት።

ተፈሪ መኰንን አልጋወራሽ ከሆኑበት ዘመን ጀምሮ ሳያቋርጡ ከዐርባ ዓመታት በላይ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴን ፍጹም በሆነ ታማኝነትና በባለሟልነት የሚያገለግሉት መኰንን ሀብተወልድ፣ የደሞዝ ቅጣት የተበየነባቸው መሆኑን የሚገልጸው የጽሕፈት ሚኒስቴር ማዘዣ ሲደርሳቸው፣ ለጊዜው ደብዳቤውን ለማመን አቅቷቸው ነበር። ከአሩሲ (ዛሬ አርሲ) አውራጃ የገበያ አሥራት ጸሐፊነት ተነሥተው፣ በአዲስ አበባ ፍልውሃ ገንዘብ ተቀባይነት አልፈው፣ የጉምሩክ ሒሣብ ሹም እስከሆኑበት እና ከዚያም በንጉሠ ነገሥቱ መንግሥት ውስጥ ከዋና ዲሬክተርነት እስከ ሚኒስትርነት ደረጃ ሲደርሱ፣ በዝርዝር የሕይወት ታሪካቸው አንድም ጊዜ በማዘዣ የደሞዝ ቅጣት ደርሶባቸው አያውቅም። ለጥቂት ደቂቃዎች ከተከዙ በኋላ፣ ምክትል ሚኒስትራቸውን አቶ ምናሴ ለማን ጠርተው፣ የደረሳቸውን ማዘዣ አሳይዋቸው። የዚያችን ቀን ታሪክ፣ ክቡር አቶ ምናሴ ለዚህ መጽሐፍ ደራሲ የነገሩት እንደሚከተለው ነበር። " .... አቶ መኰንን በቶሎ እቢሮዬ ና ብለውኝ እየተጣደፍኩ ስገባ፣ ከጽሕፈት ሚኒስቴር የተጻፈላቸውን ማዘዣ አንብበው ብለው ሰጡኝ። ልዑል አልጋወራሽ አምስት መቶ ብር የቀጧቸው መሆኑን ሳነብ ከመጠን በላይ ደነገጥኩ። እንዴት እኝህን የሚያህሉ ያገር ተቆርቋሪና የሕዝብ ወገን ሆነው ቀንና ሌሊት የሚሠሩ ሰው፣ በአንድ ብጣሽ ማዘዣ የደሞዝ ቅጣት ይወሰንባቸዋል? .... ብዬ በጣም አዘንኩ። አቶ መኰንንን ቀና ብዬ ዓይናቸውን ማየት ስለፈራሁ አቀርቅሬ ቀረሁ። ኋላ እሳቸው አነጋገሩኝ። አየህ ምናሴ! አሉኝ። አንዳንድ ጊዜ በዚህ ዓለም ባልሠራኸው ኃጢዓት ሲፈረድብህ በሕይወት መኖርህን ያስጠላሃል። የድሮ አባቶቻችን እንደ ያልጠበቁት ነገር ሲደርስባቸውና ምሬታቸውን ሲገልጡ፣ "መፈጠሬን ጠላሁት" የሚለውን ቃል የሚጠቀሙት ለካስ ወድደው አይደለም። እኔስ ግዴለም! እስከዚህ አልማረርም። የወጡት ንጉሣችን ከጉዞአቸው በሰላም እስከሚመለሱ ጥረቴን አላቋርጥም። አልጋወራሽ ይህን የወሰኑት በክፋት

ሳይሆን በየዋህነታቸው ነው። ስለዚህም አላዝንባቸውም። ማዘዣውንም ውሰድና በአግባቡ ፈጽም .... " ብለው አሰናበቱኝ።

በዚያን ጊዜ የክቡር አቶ መኰንን ሀብተወልድ ልዩ ጽሕፈት ቤት ሹም የነበረው ወንድሜ ወዳጄ አቶ አሰፋ ድፋዬ እንዳጫወተኝ፣ አልጋወራሽ በወሰዱት እርምጃ ግርማዊት እቴጌ መነንና ልዑል መኰንን መስፍነ ሐረር አዝነው የገንዘብ ሚኒስትሩን በስልክ አነጋግረዋቸዋል። ቀጥሎም ልዑል ራስ ካሣና ሊቀ ጳጳሱ አቡነ ባስልዮስ በአምሳለ ንጉሠ ነገሥት አልጋወራሽንና አቶ መኰንንን በማስታረቅ፣ የተጻፈው ማዘዣ እንዲቃጠልና ከመዝገብ እንዲፋቅ አስደረጉ። ይሁን እንጂ ይህ ሁሉ በምሥጢር የተፈጸመ እንዲሆን ቢፈለግም፣ መኰንን ሀብተወልድ አልጋወራሽን አልታዘዝም በማለታቸው በደሞዝ ቀጧቸው እየተባለ ወሬው በከተማው ተነዛ። እንደ አጋጣሚ ሆኖ በዚያኑ ሰሞን፣ የአገር ፍቅር ማህበር ያገር ባሕል ተጨዋቾች፣ "ጠቅል ቶሎ ና፣ ጠቅል ቶሎ ና የኢትዮጵያ ሕዝብ ናፍቆሀልና" እያሉ በራዲዮ ያሰሙትን ዜማ፣ አቶ መኰንን ከአልጋወራሽ ጋር በመጋጨታቸው ራሳቸው የደረሱት ዜማ ነው ተብሎ ተወራ። መቸም፣ ጨዋ የሆኑት ሰዎች ሁሉ እንደሚያውቁት፣ መኰንን ሀብተወልድን የሚያህል ትልቅ ሰው፣ ከአልጋወራሽ ጋር በሥራ ትንሽ ግጭት ስለደረሰ፣ ይህን በመሰለ ርካሽ በሆነ መንገድ ስሜታቸውን ይገልጣሉ ተብሎ አይታሰብም። በአገራችን ወሬን ፈጥሮ መንዛት የተለመደ ስለሆነ፣ በዛሬውም ሰዓት ይህንን ወሬ ምስክር አይገኝም ብለው የሚወሸክቱ መኖራቸው ታውቋል። ጠቅል ቶሎ ና የኢትዮጵያ ሕዝብ ናፍቆሀልና የተባለው ዜማ ንጉሠ ነገሥቱንና ሕዝባቸውን በስሜት ለማቀራረብ የታሰበ እንጂ፣ የቁጭት መግለጫ እንዲሆን የተዘጋጀ አይደለም። ከዚህም በኋላ፣ ንጉሠ ነገሥቱ ከረዥሙ ጉዞአቸው ወደ አገራቸው ሲመለሱ፣ ያገር ፍቅር ማህበር ዜማ ደራሲዎች በሌሉበት ጊዜ የሕዝቡን ናፍቆት እንደገለጹት ሁሉ በተመለሱበት ቀን ደግሞ፣

ኢትዮጵያ ሆይ፣ እልል በይ፣
ብርሃንሽ መጡ ግርማዊ ጃንሆይ
ብለው አዚመዋል።

ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ከሁለት ወራት በላይ በፈጀው ጉዞአቸው፣ ዩናይትድ ስቴትስንና ካናዳን፣ እንዲሁም ዩጐዝላቪያንና ግሪክን ጐብኝተው እንደ ኢ.ት.አ.ቆ. ሐምሌ 27 ቀን 1946 ዓ.ም አዲስ አበባ ሲገቡ የተደረገላቸው አቀባበል፣ ከሚጠበቅ በላይ ያማረና የደመቀ ነበር። ይህ ዕለት እንደ ሕዝብ በዓላት ተቆጥሮ፣ የመንግሥት መሥሪያ ቤቶችና፣ ትምህርት ቤቶች፣ የግል ድርጅቶችና ንግድ ቤቶች በሙሉ ዝግ ሆነዋል። ንጉሠ ነገሥቱ አዲስ አበባ ሲደርሱ፣ ከአውሮፕላን ማረፊያው ጀምሮ እስከ አፄ ምኒልክ ቤተመንግሥት ድረስ፣ የአዲስ አበባና የአካባቢዋ ነዋሪዎች፣ ተማሪዎችና ወታደሮች በየመንገዱ ግራና ቀኝ ተሰልፈው፣ በጭብጨባና በሆታ የተደረገላቸው አቀባበል እጅግ የሚያስደስት ሆኖ ነበር።

በዚያች ሐምሌ 27 ቀን 1946 ዓ.ም ጠዋት ኃይለኛ ዝናብ ሲጥል ካረፈደ በኋላ፣ ጃንሆይ ከገቡበት ሰዓት ጀምሮ ታላቁ ቤተመንግሥት እስኪደርሱ፣ ዝናቡ ቆሞ ፀሐይ በመውጣቱ፣ ለሕዝቡ አቀባበል የተመቸ ሆኖ ነበር። በዚያን ዕለት በአውሮፕላን ማረፊያው ሜዳ የጃንሆይ ልዩ አውሮፕላን እስኪያርፍ ድረስ፣ ልዑል አልጋወራሽ በጄኔራልነት የጦር ልብስ ቀበቶ ታጥቀውና ፋራዥር አንዝርግገው፣ በራስ አበበና በአቶ መኰንን ሀብተወልድ ግራና ቀኝ ታጅበው በጋለ መንፈስ ሲጨዋወቱ የነበረውን ሁኔታ የዚህ መጽሐፍ ደራሲ በራዲዮ ሪፖርተርነቱ ያየውን ያስታውሳል።